

የኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዴሚ
የሳይንስና ቴክኖሎጂ ቃላት ስያሜ ፕሮጀክት

ACADEMY OF ETHIOPIAN LANGUAGES
SCIENCE AND TECHNOLOGY TERMS TRANSLATION PROJECT

# የአማርኛ የህክምና መዝገበ ቃላት

# AMHARIC DICTIONARY OF MEDICAL TERMS

የኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዳሚ
የሳይንስና ቴክኖሎጂ ቃላት ስያሜ ፕሮጀክት

ACADEMY OF ETHIOPIAN LANGUAGES
SCIENCE AND TECHNOLOGY TERMS TRANSLATION PROJECT

# የአማርኛ የህክምና መዝገበ ቃላት
# AMHARIC DICTIONARY OF MEDICAL TERMS


አዘጋጆች * ቴቶ ላኪሳ
** ፍቅሬ ዴንግል በየነ
ሰሎሞን ሀረገወይን
* ሰይፉ ዳንኤል



1978
አዲስ አበባ

1986
ADDIS ABABA


---

* በቃላት ትርጉማው ብቻ የተሳተፉ
** ለተተረጐሙት ቃላት ማብራሪያ በመስጠት ብቻ የተሳተፉ

## ማሳሰቢያ

ይህ መዝገበ ቃላት በተቻለ መጠን ከፍተኛ ጥረት ተደርጎበት የተዘጋጀ ሲሆን፣ በኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዳሚ ጉባኤ ወደፊት ገና የሚፀድቅ መሆኑን እያሳሰብን በመዝገበ ቃላቱ ላይ ገንቢ አስተያየት ለመስጠት የሚፈልግ ሁሉ ቀጥሎ ባለው አድራሻ አስተያየቱን በፅሁፍ ሊሰጥ የሚችል መሆኑን እንገልፃለን።

የኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዳሚ
ፖ.ሣ.ቁ. 1907
ባህል ሚኒስቴር
አዲስ አበባ

## ይዘት CONTENT

## ምስጋና

ለዚህ ለሳይንስና ቴክኖሎጂ ቃላት ፕሮጄክት አስፈላጊውን የገንዘብ እርዳታ ላደረገው ለተባበሩት መንግስታት የሳይንስና ቴክኖሎጂ ለልማት ፋይናንሻል ሲስተም (UNFSSTD) የኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዳሚ ከፍተኛ ምስጋና ያቀርባል።

## ACKNOWLEDGEMENT

The Academy of Ethiopian Languages expresses its profound gratitude to the United Nations Financial System for Science and Technology for Development (UNFSSTD) for sponsoring this project (STTTP)

## መቅድም

ይህ የህክምና የአማርኛ መዝገበ—ቃላት የኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዳሚ የሳይንስና ቴክኖሎጂ ቃላት ስያሜ ፕሮጀክት ካዘጋጃቸው 13 መዝገበ—ቃላት መካከል አንዱ ነው:: በአጠቃላይ በፕሮጀክቱ የተዘጋጁት የሳይንስና ቴክኖሎጂ ስያሜ መዝገበ—ቃላት ከዚህ በታች ለተመለከቱት የሙያ ዘርፎች ሲሆን፤ ምንጭ ቋንቋውም / Source Language / እንግሊዝኛ ነው::

1. ግብርና - AGRICULTURE
2. ቦታኒ - BOTANY (BIOLOGY I)
3. ህንፃ ኮንስትራክሽን - BUILDING CONSTRUCTION(TECHNOLOGY I)
4. ኬሚስትሪ - CHEMISTRY
5. ኤሌክትሮ ሜካኒክስ - ELECTRO-MECHANICS
6. ጂኦግራፊ - GEOGRAPHY
7. ጂኦሎጂ - GEOLOGY
8. ማቲማቲክስ /ማቲማቲካ/ - MATHEMATICS
9. ህክምና - MEDICINE
10. ኑትሪሽን - NUTRITION
11. ፊዚክስ /ፊዚካ/ - PHYSICS
12. ስታቲስቲክስ/ ስታቲክስቲካ/ - STATISTICS
13. ዞኦሎጂ - ZOOLOGY

እነዚህ በፕሮጀክት ደረጃ የተሰሩት የሳይንስና ቴክኖሎጂ ስያሜ መዝገበ ቃላት የመደበኛ የመዝገበ ቃላት አሰራርን ዘዴ ሙሉ በሙሉ በመከተል ሳይሆን በየሙያው ዘርፍ የተሰየሙትን አዳዲስ ቃላት ለማስተዋወቅና ለማብራራት አመቺ በሆነ የአሰራር ስልት እያንዳንዱን ስያሜ በፊደል ተራ በማስገባት ነው:: ስለሆነም የተሰየሙት ቃላት አመቺ በሆነ መድረክ ተሰራጭተውና ተፈትነው ተቀባይነት ያገኙትና በአካዳሚው የፀደቁት ወደፊት በመደበኛ የመዝገበ ቃላት አሰራር በአንድነት ተጠቃለው የሳይንስና ቴክኖሎጂ ስያሜ መዝገበ ቃላት በሚል ርእስ ታትመው ይወጣሉ:: ይህ መዝገበ ቃላትና ሌሎቹም ቀጥለው የተመለከቱትን 3 ዋና ዋና ክፍሎች ይዘው ይገኛሉ::

1. የቃላት ማብራሪያ ክፍል
2. የአማርኛ—እንግሊዝኛ የቃላት ዝርዝር
3. የእንግሊዝኛ—አማርኛ የቃላት ዝርዝር

የቃላት ማብራሪያው ክፍል በየሙያው ዘርፍ ስያሜ ከተሰጣቸው አጠቃላይ ቃላት ውስጥ ሃምሳ በመቶውን ያህል መርጦ የቃላቱን ፅንስ ሃሳብ በአረፍተ ነገርና አስፈላጊም በሆነበት ቦታ በስእል አማካኝነት የሚገልፅ ክፍል ነው::

በየሙያው ዘርፍ ከተሰየሙት ቃላት ውስጥ ሃምሳ በመቶው ብቻ ተወስና የተብራራበት ዋናው ምክንያት ቀደም ሲል እንደተገለፀው የተሰየሙት ቃላት በስራው ተሰራጭተውና ተፈትነው ተቀባይነት ከማግኘታቸውና ከመፅደቃቸው በፊት ሁሉንም ማብራራት አስፈላጊ ባለመሆኑ ነው:: ስለሆነም ከላይ ከተጠቀሰው የሳይንስና ቴክኖሎጂ ስያሜ መዝገበ ቃላት ታትሞ በሚወጣበት ጊዜ ዋናና ወሳኝ የሆኑት ስያሜዎች ሁሉ ይብራራሉ:: በየሙያው ዘርፍ መዝገበ ቃላት ውስጥ ምን ያህል እንደተሰየሙ ለማሳየትና ልዩ ልዩ ሳይንስና ቴክኖሎጂ ነክ ፅሁፎች በአማርኛም ሆነ በእንግሊዝኛ በሚነበቡበት ጊዜ አቻ ስያሜዎችን ለማወቅ እንዲረዳ በየመዝገበ ቃላቱ ውስጥ የአማርኛ—እንግሊዝኛ፣ የእንግሊዝኛ—አማርኛ የቃላት ዝርዝር ይገኛል::

አንዳንድ የእንግሊዝኛ ስያሜዎች የአማርኛ አቻ ስያሜ በየሙያው ዘርፍ በሚሰጧቸው ወቅት በልዩ ልዩ ቃላት ተሰይመው ይገኛሉ:: በአንፃሩም ለተለያዩ የእንግሊዝኛ ስያሜዎች አንድ የአማርኛ ስያሜ የሚያገለግልበት ሁኔታ በየመዝገበ ቃላቱ ዝግጅት ውስጥ ተከስቷል::

ከዚህም በቀር ለአንድ የእንግሊዝኛ ስያሜ ሁለትና ሶስት አማራጭ ስያሜዎች አልፎ አልፎ በየመዝገበ ቃላቱ ውስጥ ተሰጥቶ ሲገኝ ለዘለቄታው ተቀባይነት የሚያገኘው ስያሜ ወደፊት ጊዜ ይፈታዋል::

በፕሮጀክቱ የስራ ሂደት ወቅት በየሙያው ዘርፍ የአማርኛ ስያሜ የተሰጧቸው ቃላት ዝርዝር እየተባዛ ለአስተያየት በየስፍራው በመሰራጨቱ ከግለሰቦችና ድርጅቶች በተገኙ ገንቢ አስተያየቶች አንዳንድ የስያሜ ለውጥ ከመደረጉም በላይ፣ ፕሮጀክቱ በየጊዜው ባካሄዳቸው ዎርክሾፖችና ሴሚናሮች የስያሜ ማሻሻልና ለውጥ ተደርጓል:: ሆኖም በየጊዜው የተደረጉትን አንዳንድ የስያሜ ለውጦች በትክክል በሚገኙበት ቦታ ሁሉ ለማረም አዳጋች በመሆኑ፣ በዚህና በሌሎቹም መዝገበ ቃላት ውስጥ ሊገኝ የሚችል አንዳንድ የስያሜ መዘበራረቅ ወደፊት የሳይንስና ቴክኖሎጂ ስያሜ መዝገበ ቃላት በሚዘጋጅበት ጊዜ ጥራት ያገኛል::

በኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዳሚ የሳይንስና ቴክኖሎጂ ቃላት ስያሜ ፕሮጀክት የተሰየሙት ቃላት በአጠቃላይ ከ15,000 በላይ ሲሆኑ፣ አብዛኛዎቹ ስያሜዎች የሁለተኛ ደረጃንና የአንደኛ ዓመት የዩንቨርስቲ ትምህርት በአማርኛ ቋንቋ ለመስጠት የሚያስችሉ መሆናቸው ይታመናል::

በየሙያው ዘርፍ ጥቂት የናሙና ምንባቦች ፕሮጀክቱ አዘጋጅቶ ለሙከራ አውጥቷል::

የፕሮጀክቱ ዲሬክተር
አሰፋ ገብረማርያም ተሰማ
የኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዳሚ ዋና ፀሃፊ

የፕሮጀክቱ የቴክኒክ አስተባባሪዎች
ኤርሚያስ ዳኜ /ዶ.ር/
ደምሱ ገመዳ /ዶ.ር/

## መግቢያ

በዚህ የአማርኛ የህክምና መዝገበ ቃላት ውስጥ በአጠቃላይ ከ1.400 በላይ የሚሆኑ የህክምና ተግባር፣ መሣሪያና ልዩ ልዩ ጉዳዮች የሚገልጹ ቃላት ነጠላ ትርጉም የተሰጣቸው ሲሆን ከእነዚሁ ውስጥ 508 ቃላይ የማብራሪያ ትርጉም ተሰጥቷቸው ይገኛሉ። ከዚህ መግለጫ እንደሚታየው በርከት ያሉት ቃላት የማብራሪያ ትርጉም ያለ ተሰጣቸው መሆኑ ግልጽ ነው። ይህም ሊሆን ከቻለባቸው ምክንያቶች አንዱ በህክምና መስክ ከሚሰራባቸው ቃላት ከሌሎቹ እንደ ቦታኒ(Botany)ዙኦሎጂ(Zoology) በመሳሰሉት ዘርፎች ውስጥ የማብራሪያ ትርጉም ተሰጥቷቸው ስለሚገኙ ነው፣

ምሳሌ፣

| | | | |
|---|---|---|---|
| Tissue | = | ህብረህዋስ | (Botany) |
| Cell | = | ህዋስ | " |
| Virus | = | ረቂቅ | " |
| Herbalist | = | ስርማሽ ሃኪም | " |
| Simple microscope | = | ነጠላ ማይክሮስኮፕ | " |
| Nucleus | = | ኑክለስ | " |
| Glycolysis | = | ፍርሰተግሉኮስ | " |
| Glucose | = | ግሉኮስ | " |

ይህ የህክምና መዝገበ ቃላት ሲዘጋጅ የቃላቱን ነጠላ ትርጉም በመሰየም ረገድ የተለያዩ ስልቶችን አዘጋጆቹ መጠቀማቸውን ከቃላቱ አቀማመጥ መረዳት ይቻላል። ለናሙና ያህልም የሚከተሉትን ስልቶች ጠቅሰን በሚከተለው ሁኔታ እናሳያለን።

<u>አንድ ለአንድ</u> /ትርጉም/

በዚህ ዓይነቱ የትርጉም ስልት ለአንድ የእንግሊዝኛ ቃል አቻውን አንድ የአማርኛ ቃል በመስጠት የተተረጎመ ነው፣ ይህም የሚከተለውን ይመስላል፣

| | | |
|---|---|---|
| Neonate | = | ህንጠ |
| Corex | = | ልሀፀ |
| Thrombus | = | ልጋጽ |
| Esophagus | = | ወስቄ |
| Quarantine | = | ቀባ |
| Lochia | = | አራስፍስ |
| Febrile | = | አትኩሽ |
| Cirrhosis | = | ኩምትሬ |

## ሁለት ለአንድ /ትርጉም/

በዚህ ዓይነቱ የትረጉም ስልት ለአንዱ የእንግሊዝና ቃል ሁለት የአማርኛ ቃላት ወይም ለአንዱ የአማርኛ ቃል ሁለት የእንግሊዝና ቃል በመስጠት የተተረጉሙ ሀኑው ይገኛሉ፤ ይህም የሚከተለውን ይመስላል።

Epiphysis = ህፃን አፅም
Carilage = ልም አፅም
Dysuna = ሽንት ማጥ
Hooping Cough = ትክትክ
Mediastinum = ንፍቀ ደረት
Ascending infection = አራጊ ልክፍት
Aorta = አቢይ ደምሳጅ
Typhoid = አንጀት ተስቦ
Metacarpal = አፅመ መዳፍ
Vermix Coseosa = አሙካ
Nipple = ጡት ጫፍ

## ሁለት ለሁለት /ትርጉም/

በዚህ አይነቱ የትርጉም ስልት ውስጥ ጥምር የሆኑት የእንግሊዝና ቃላት ማለትም ከሁለት ቃላት ተወጣጥተው አንድ አዲስ ቃል መሥርተው በሚገኙበት ጊዜ፣ እነዚያን ቃላት ለመተርጎም በተቻለ መጠን ነጠሏ የአማርኛ ቃል ተፈልጎ ሲታጣ፣ በተመሳሳይ መንገድ የአማርኛውም ቃል ከሁለት ቃላት የተጣመረ ቃል እንዲኖረው በማድረግ የትርጉም ሥራ ተከናውኗል፣ ይህም እንደሚከተለው የመሰለ ነው።

Passive Immunity = ህላፊ መድህን
Bronchial Asthma = ቀሰቢት አስም
Aminotic fluid = ሽንት ውሃ
Nervous system = ነርቫዊ ቀንበር
Mucous Membrane = ንፋጭ ገለፈት
Venerial disease = አባለዘር በሽታ
Mons pubis = ጭገር ዲብ
Nasogastric tube = ሕ.ንፈከርስ ቱብ

## ቃል በቃል /ትርጉም/

በዚህ የትርጉም ስልት ለመጠቀም ሁለት የጎሉ ምክንያቶች አሉ። አንደኛው ቃል በጣም የተለመደ ሲሆን ነው፣ ሁለተኛው ለቃሉ አጥጋቢ የሆነ አቻ ቃል ሲታጣ ሲሆን ለምሳሌም ያህል የሚከተሉት ማስረጃዎች ተጠቅሰዋል።

| | | |
|---|---|---|
| Hormon | = | ሆርሞን |
| Schistosoma | = | ሽስቶሶማ |
| Shigella | = | ሺጌላ |
| Thermometer | = | ቴርሞሜትር |
| Anatomy | = | አናቶሚ |
| Acid | = | አሲድ |
| Allergy | = | አለርጂ |
| Alicali | = | አልካሊ |
| Amoeba | = | አሜባ |
| Eclampsia | = | ኤክላምፕሲያ |
| Cancer | = | ካንሰር |
| Cholera | = | ኮሌራ |

**የመነሻ ምዕላድ መጠቀም**

የዚህ ዓይነቱ የትርጉም ስልት፣ ስነ... ፀረ... የተባሉትን የመነሻ ምእላዶች የተደረገው የትርጉም ክንዋኔ ነው። ይህም በሚከተሉት ምሳሌዎች ይታያል

ስነ...

| | | |
|---|---|---|
| ስነመነሻ | = | Etiology |
| ስነማእስ | = | Dermatology |
| ስነአይን | = | Ophtalmology |
| ስነፅንስ | = | Obstetrics |

ፀረ...

| | | |
|---|---|---|
| ፀረ ሂስታሚን | = | Antihistamine |
| ፀረ ህመም ልክፊት | = | Disinfectant |
| ፀረህዋስ | = | Antiseptic |
| ፀረሱም | = | Antitoxin |
| ፀረአንግዓካል | = | Antibody |

ኢ... /አሉታ/

በአዎንታ ቃላት ላይ የአሉታ ምልክት የሆነችውን "ኢ" የተባለችውን በስተመነሻ በመጠቀም ከዚህ ቀጥሎ ለአስረጅነት የተጠቀሱትን የመሳሰሉት ቃላት እንዲተረጐሙ ተደርጓል::

| | | |
|---|---|---|
| ኢሸርሸርታ | = | Indigestion |
| ኢፈ ቃደምግብ | = | Anorexia |

የግዕዝ ቃላት

ሙሉ በሙሉ የግዕዝ ልሳን ቃላት የሆኑ እስከዛሬም አንዳንዶቹ ያልተለመዱ ወይም ያልተሰሙ ይሆናሉ ተብለው የሚገመቱ በዚህ የትርጉም ሥራ ውስጥ ገብተው ይገኛሉ:: ከዚህ ቀጥሎ ከተጠቀሱት ምሳሌያች መመልከት ይቻላል::

| | | |
|---|---|---|
| አማሬ | = | Demonistration |
| አስኬት | = | Penis |
| ፀዋሪ | = | Carrier |
| ወሬዛ | = | Adolescent |
| አንዚራ | = | Vocal Cord |
| ህፀነ አፅም | = | Epiphysis |

ከፍ ብሎ የተጠቀሱትን ልዩ ልዩ የትርጉም ስልቶች የተከተልንበት ምክንያት እንደ ቃላቱ የፍች ባህርይ ተስማሚነት አማራጭ በመፈለግና የተሻለውንም፣ ማለትም ለአንባቢም ለአድማጭም አቻ ሊሆን ይችላል ብለን ያሰብነውን አማራጭ ለመያዝ በመሞከር ነው፡፡

የማብራሪያ መግለጫዎች በተቻለ መጠን አጭር ምጥን እንዲሉ ቢደረጉም፣ ግልፀ በሆነ መንገድ የፅንሰሃሳቡን ምንነት እንዲያስጨብጡ ለማድረግ ከፍተኛ ትኩረት ለመስጠት ተሞክሯል:: ይህንኑ የፍች ግልፀነት የተሟላ ለማድረግ አስፈላጊ ሆኖ በተገኘበት ቦታ የሥዕል መግለጫ ተሰጥቷል:: እንደማብራሪያዎቹ ቃላት ሁሉ እንዲሁም ሥዕሉ ግልፅና ትክክለኛ እንዲሆን ጥረት ተደርጓል::

የማብራሪያ መግለጫዎችንና ሥዕሎችን ለመምረጥ በዚሁ በህክምና ሙያ ቃላት ላይ የተዘጋጁ የእንግሊዝኛ መዝገበ ቃላት በጣም ረድተውናል::

በዚህ መዝገበ ቃላት ውስጥ የቀረቡት ስእሎች በሙሉ የተዘጋጁት በተማሪ ታረቀኝ አበበ ነው::

ከአዘጋጆቹ
ፍቅረድንግል በየነ
ሰሎሞን ሃረገወይን /ዶ.ር/

# የአማርኛ የህክምና መዝገበ ቃላት

# AMHARIC DICTIONARY OF MEDICAL TERMS

# ሀ

ሀላፊ መድሀን Passive Immunity

ገቢር ወይም ንቁ ያልሆነ፣ የተዘጋጀ ፀረንገዳካላን በመውጋት በሽታን መከላከል::

ሀሞት Bile

ቢጫ ወይም አረንጓዴ ቀለም ያለው መራራ ከጉበት የሚመነጭ ለስብና ቅባት ምግቦች አንሸርሸረት የሚጠቅም ፈሳሽ:

ሀሞት ከረጢት Gall bladder

በሰው ላይ ከጉበት ስር ተለጥፎ የሚገኝ ሀሞት ለማጠራቀም የሚጠቅም ፊኛ::

ሀሞት ከረጢት ሰከፈት Cholecystitis

የሀሞት ከረጢት መበገን::

ሀይጅን Hygeine

ስለ ጤና አጠባበቅ ጥናት፣ ሀገችን የማስተዋልና የማክበር ዘዴ::

ሄሞግሎቢን Hemoglobin

በቀይ ደም ሀዋስ ውስጥ የሚገኝ ብረት አዘል ሀመለማሉ፣ ስራው ኦክስጂንን ከሳንባ ተሸክሞ ወደ ቀረት የሰውነት ሀብረ ሀዋሳት ማዳረስ:: ከሰው አንድ መቶ ሲሲ ደም ውስጥ ከ14 እስከ 16 ግራም ይገኛል::

ሀገጠ Neonate

አዲስ የተወለደ ሀፃን እስከ አራት ሳምንታት እድሜ የሚጠራበት ስያሜ::

ሀክምና Medicine

በሽታን የመከላከል፣ ሀመምተኛን ማስታመምና የመንከባከብ ዘዴ::

ሀዋስሞት Necrosis

በደም እጦት፣ በጉዳት፣ በኬሚካላዊ ነገሮችና የባክቴሪያ መርዞች ምክንያት በተወሰነ ቦታ የሀብረሀዋስ ሞት::

ሀፃን Infant

ከሀገጠነት እስከ ሁለት አመት እድሜ ድረስ ያለ ለጋ ልጅ::

ሀፀነአፀም Epiphysis

የረጃጅም አጥንቶች አናትና ገርጓ ክፍል::

ሀርሞን Hormone

ከሰውነት አባላካል ወይም እጢ የሚመነጭ ኬሚካዊ ለዩ ቅስ፣ በደም አማካይነት ወደ ሌሎች የሰውነት ክፍሎች በመጓዝ ሌሎች የሰውነት ክፍሎች ስራና ምገጪት የሚያነሳሳ::

ሆዳዊ Abdominal

የሆድ የሆነ፣ ሆድን የሚመለከት ሁሉ::

ሆድ Abdomen

ከድሌሽና ከዳሌ ገንዳ መሀከል ያለ ጋታ ጨጓራ፣ አንጀት፣ ጉበት፣ ሃሞት ከረጢት፣ ጣፊያ፣ ኩላሊት፣ ኩሊትን፣ እጢንና ፊኛን የሚይዝ::

ሆድ ትል Helmenth

በጥገኝነት ወይም በነፃ ኑሮ በአንጀት ውስጥ የሚገኝ ትል መሰል ተዋሲይ::

ሆድ እጥበት Enema

በፈሳሽ ደንዳኔን ለማጠብ የሚከናወን ድርጊት።

ሆድ ድርቀት Constipation

ሰገራን አዘውትሮ ለመውጣት አለመቻል።

ለ

ለስላሳ ላንቃ Soft palate

እንጥል የተጣበቀበት ጠንካራ ያልሆነውና በስተኋላ በኩል ያለው የላንቃ ክፍል።

ለኩሽ Rabies

ስጋ በል የሆኑ እንስሳት/ውሻ፣ ድመት፣ ተኩላ፣ ቀበሮ/ በቫይረስ አማካይነት የሚመጣ አጣዳፊና ወደ ሰው የሚተላለፍ በሽታ፣ የእብድ ውሻ በሽታ።

ለጋስ Donor

ደሙን ወይም ክፍለአካሉን ለሌላ ሰው በፍላጎት የሚሰጥ ግለሰብ።

ላብ Sweat

በቆዳ ውስጥ ከሚገኙ የላብ እጢ የሚወጣ ጨዋማ ፈሳሽ።

ላንቃ Palate

የአፍንና የአፍንጫን ገታዎች የሚለይ አግዳሚ ከፊት ጠንካራ ከኋላ ለስላሳ የሆነ የአፍ ጣሪያ።

ላንቃ እጢ Tonsil

ከፍርንታዊ ህብረ ህዋስ የተሰራ በሰርን ግራና ቀኝ ስርጉድ ውስጥ የሚገኝ እጢ።

ላንገርሃን ደሴቶች Islands of Langerhan

በመረጭ እጢ ውስጥ ያሉ ስብስብ ህዋሳት ከነዚህም ሶስት አይነት ህዋሳቶች አንደኛው ኢንሱሊን ያመነጫል የነዚህ ደሴቶች መደምሰስ ወይም መድከም የስኳር በሽታን ያመጣል።

ላእላይ Superior

የአካል የላይኛው ክፍል ወደላይ ያለ።

ላእላይ መንጋጋ Maxilla

የላይ ጥርሶች የሚሰኩበት የላይኛው የመንጋጋ አጥንት።

ላእላይ ማእሰ Epidermis

ደም ስር የሌለበት የቆዳ የውጪኛው ክፍል

ሏሀፀ Cortex

ውጫዊ የሆነ የማንኛውም አካላካል ቅርፊት።

ልመት Viscrea

በሰውነት ውስጥ የሚገኝ አካላካል በተለይም በሆድ ውስጥ የሚገኝ የሆድ እቃ።

ልማፀም Cartilage

እንደ ጆሮ አፍንጫና የጎድን አጥንት ጫፍ የመሳሰሉ የአካል ክፍሎች ውስጥ የሚገኝ ለስላሳ አጥንት።

ልምሾ Paralysis

ጊዜያዊ ወይም ቋሚ የሆነ የሰውነት ክፍለአካል መደንዘዝ በተለይ ስሜት መጥፋት /ቸዛካል/ እንዲሁም ሰውነትን ለመቆጣጠር መሳን /ሽባነት/።

ልባስ Serosa

ልም አባላካላትን የሚሸፍን ብሬና።

ልባድ Epithelium

ቆዳንም ሆነ ንፋስ ወይም ልስልስ ገለፈቶችን በላይ መልካቸው የሚሸፍን የህዋስ ኅብርብር ወይም ልባስ።

ልብ Heart

ከሞቱር ረገብ በማለት ደም በሰውነት ውስጥ የሚሰራጭ አራት ጎታዎች ያሉት የደምዑደት ቀንባር ማእከል /ስእለ ተመልከት/።

ልብ ድካም Heart failure

በተለያዩ ምክንያቶች ምሳሌ፣ ከፍተኛ የደም ግፊት መጠን፣ የልብ ክፍክድ መጥ በብ ወይም መስፋት ወዘተ. ልብ ተገቢውን የደም ማስተላለፍ ተግባር ማከናወን ሲሳነው ምልክቶቹ በመጠነኛ እንቅስቃሴ ትንፋሽ ማጠር ውሃዘል ገላ ወዘተ ሲሆኑ፣ የግራ ወይም የቀኝ ልብ ክፍል ሊደክም ይችላል።

ልብ ጡንቻ Myocardium

የልብ ጡንቻ ህብረ ህዋስ።

ልክፍታምጪ Pathogen

በሽታን የሚያመጡ ጥቀን ዘአካላት።

ልጋድ Thrombus

የደም ስርን ወይም የልብን ወና የሚዘጋ የረጋ ደም።

ሉቲናፍጊ ሆርሞን Lutenizing hormone

እንቁልጢ ላይ ያለ ሉቲንገላ እንዲያድግ የሚረዳ ከፊተኛ /ቀዳማይ/ አዕይ እጢ የሚመነጭ ሆርሞን።

## መ

መሃንነት Sterility

ልጅ ለመውለድ ወይም ለማስወለድ አለመቻል።

መምገል Suppuration

መግል የመፍጠር ሁኔታ።

መምጠጥ Absorb

ማንኛውንም ልዩ ቁስ በፍርንት ስር ወይም በደም ስር ወደ ሰውነት ማስገባት።

መምጠጥ Aspiration

ፈሳሽን በመምጠጫ መሳሪያ ከማንኛውም ጎታ ማስወገድ።

መርመሬ Peritoneum

ውስጠ ሆድንና የሆድ ዕቃዎችን የሚሸፍን ልባስ።

መርፌ Injection

በደም ስር በተለይ በደመላሽ በጡንቻ በቆዳ ስር ወይም ውስጥ ወዘተ ፈሳሾችን በመርፌ መወጋት።

መሰራጨት Disseminate

በአባላካል ወይም በሰውነት ውስጥ መበተን ወይም መረጨት።

መሰብሰብ Adduction

የሰውነትን ቅርንጫፍ አካል ወደ ሰውነት ማእከላዊ መስመር ማስጠጋት።

መሳምዝ Autoclave

ግፊት ባለው የሞቀ እንፋሎት የህክምና መሳሪያዎችን ባክቴርያ አልባዊ ማድረጊያ መሳሪያ።

መሰቆ Esophagus

ምግብ የሚወርድበት ከማንቁርት እስከ ጨጓራ ያለው ቱቦ። ጕሮሮ ስእል ተመልከት

መሰቀር Trocar

ከጉታ ውስጥ ፈሳሽን ለማውጣት የሚያገለግል ሹል ጫፍ ያለው መሳሪያ

መሰተሃውር Vagus

ስሜታዊና አንቀሳቃሽ የደም ስሮች ያሉት ሰፋ ያለ ስርጨት ያለው አስረኛው የራስ ነርቭ።

መቀርደድ Laceration

የተገዘገዘ ጠርዝ ያለው ቁስል።

መቀፍቀፊያ Incubation

ያለጊዜው የተወለደ ህፃንን በተስተካከለ ሙቀት ማሳደጊያ መሳሪያ።

መቅን Bone marrow

በቅልጥም አጥንቶች ውስጥ የሚገኝ ቅባትነት ያለው ለስላሳ ልዩ ቅስ።
መቅን ቀይ ወይም ቢጫ ሊሆን ይችላል

መባለቅ Puberty

የመራቢያ ብልት ተግባሩን የሚጀምርበት ጊዜ ከ12 እስከ 16 ዓመት ድረስ ያለው ጊዜ።

መተንፈስ Breathe

አየርን ወደ ሳንባ አስገብቶ ማስወጣት።

መታፈን Asphyxia

የሳይናው የአስተንፋስ ቱቦ በመዘጋት ወይም መተንፈስ በማቃቱ ምክንያት የሚደርስ የአየር እጦት።

መንገጭአጢ Parotid Gland

ምራቅ ከሚያመነጩት አጢዎች ከፍ ያለውና በመንጋጋ ገን የሚገኝ።

መንጋጋ ቆልፍ Tetanus

የሚያስቃይ የጡንቻ መኮማተርን የሚያመጣ ቴታነስ ባሲለስ በተባለ ባክቴሪያ መርዝ የሚደርስ አጣዳፊ ልክፈት።

መንገል Cannula

ከብረት ወይም ኘላስቲክ የተሰራ ቱባ በሰውነት ውስጥ ፈሳሾችን ለማውጣት ወይም ለማስገባት የሚጠቅም። ብዙውን ጊዜ መንገልን ያለችግር ለማስገባት በቱቦው ቀዳዳ ውስጥ መሰቀር ይገባበታል።

መንጠባጠብ Driube

የፈሳሽ /ምሳሌ ሽንት/ በትንሽ በትንሹ ከቁጥጥር ውጭ መፍሰስ። መዝረብረብ

መኮማተር Spasm

ያለውዴታ የጡንቻ በድንገት መሰብሰብ

መኮማተር Contraction

የጡንቻ ወይም የጠባሳ መሰብሰብ የሚያስከትለው መሰብሰብ ወይም መጨማተር።

መውለድ Delivery

ሽልን የመውለድ ተግባር ዓፄን ከናቱ ማህፀን የሚወጣበት ሁኔታ መገላገል።

መዘራጋት Abduction

ከሰውነት ማእከላዊ መስመር የሰውነት አካልን ማለት ምሳሌ፣ እጅን ወደ ውጭ
መዘርጋት።

መዳፍ Palm

በፊትለፊት በኩል ያለው ከአምባር እስከ ጣቶች ድረስ ያለው የእጅ ክፍል።

መድሃኒት Medicine

በሽታን ለመከላከል ወይም ለማከም የሚጠቀም መፈወሻ።

መድሃኒት ልክ Dose

በአንድ ጊዜ የሚወሰደው የመድሃኒት መጠን።

መድህን Immunity

ለጉዳት በተለይ ለመርዞች፣ ለባእድ ፕሮቲኖችና ለወራሪ ጥገኞች አለመበገርና
የመመከት ሁኔታ።

መድማት Hemorrhage

ከሰውነት ወደ ውስጥ ወይም ወደውጭ ደም መፍሰስ።

መገርጣት Pallor

በልዩ ልዩ ምክንያቶች /ምሳሌ በሃደም/ የቆዳና በውጭ የሚታዩ ንፋጭ
ገለፈቶች /ምሳሌ የአፍ ውስጥ ቀንደብ/ ቀለም ነጣ ማለት።

መግሊት Pustule

እንደ ብጉር ያለና በቆዳ ላይ ትንሽ መግል ወይም ፍርንት ፋስ የያዘ እብጠት።

መግል Pus

በሕብረህዋስ ልክፈት ምክንያት የሞቱ ነጭ ደም ህዋሳት፣ ባክቴርያዎች፣ ተወጋጅ
ሕዋሳትና ሕዋስ ፈሳሽን የያዘ ቢጫ መልክ ያለው ፈሳሽ።

መጨረሻ Terminal

ከአካል የመጨረሻው ክፍል ወይም የነገር ሁሉ ማለቂያ።

መፋሰሻ Lumen

በደምላሽ፣ ደምሳጅ፣ አንጀት፣ ወዘተ... ቱቦዎች ውስጥ ያለው ክፍተት።

ሚላወስ Motile

በገዛ ራሱ ለመንቀሳቀስ የሚችል።

ሚክርባልባ /ብልሀት/ Aspetic Technique

ነፍሳትን ለማጥፋት የሚደረግ /ዘዴ/።

ሚክሮባልባዊ Aseptic

ከጥቃቅን ነፍሳት ነፃ የሆነ።

ማሀል ጆሮ ብግነት Otitis Media

ከጆሮ የመሀከለኛው ክፍል ከጆሮ ታምቡር በስተውስጥ ያለው መለከፍና መብገን።

ማህፀን Uterus

በጡንቻ ሀብረ ህዋስ የተሰራ ሶስት ማእዘን ቅርፅ ያለው ፅንስና ሽል የሚያድግበት የሴት የዘር አባላካል፣ የሽል ማደጊያ።

ማህፀን ቱቦ ብግነት Salphingitis

የፋሎፕ ቱቦ በባክቴርያዎች መለከፍ።

ማህፀን አናት Uterine fundus

ማህፀን ቱቦዎች ከማህፀን ጋር ከሚገናኙበት በላይ ጎብ ብሎ የሚገኘው የማህፀን ክፍል።

ማህፀን ገላ Uterine body

ሰፋ ያለውና የላይኛው የማህፀን ክፍል።

ማህፀን ጡንቻ Myometrium

የማህፀን ጡንቻ ሀብረሀዋስ።

ማርከሻ Antidote

መርዝን የሚበርዝ የሚያወም መድሃኒት።

ማስወረድ Abortion

ወቅት ወይም ጊዜው ሳይደርስ የሁኔታ መጨናገፍ፣ ያረገዘ ማህፀን ሃያ ስምንት ሳምንት ሳይሞላው የፅንሱ መውጣት። ውርጃ

ማስገድ Excretion

ከሰውነት ውስጥ እንደሰገራ፣ ሽንት፣ ላብ፣ አክታ የመሳሰሉትን ተወጋጅ ነገሮች ማስወጣት።

ማቅለሽለሽ Nausea

ለማስታወክ ያለ ዝንባሌ፣ ከማስታወክ በፊት ማጥወልወልና የሆድ መረበሽ ስሜት።

ማብላላት Digestion

በቅንባር ለውጥ ሜካኒካዊና ኬሚካዊ ሂደት የምግብ መፈጨትና በቀላሉ ወደ ሰውነት ውስጥ ሰርጎ ለመግባት መዘጋጀት።

ማንቱ ምርመራ Mantoux's test

በቆዳ ስር የሚወጋ ካረጀ ቱበርኩሊን የሚዘጋጅ ከትባት፣ የነቀርሳ በሽታ በበሽተኛው ላይ ካለ የተከተበበት አካባቢ ከሃያ አራት እስከ ሰባ ሁለት ሰአት ድረስ ቀልቶ ይጠጥራል።

ማእዘር Radius

ውጫዊውና አጠር ያለው የክንድ አጥንት።

ማከም Medication

መድሃኒቶች በመስጠት በሽታን ማከም።

ማያ ነርቭ Optic Nerve

ሁለተኛው የራስ ቅል ነርቭ የሆነና ለማየት የሚጠቅም የልዩ ስሜት አባላካል።

ማዳመጥ Ausculation

የውስጥ አባላካላት የሚሰጡትን ድምፅ በመስማት የሚደረግ የምርመራ ዘዴ::

ማዳመጫ Stethescope

በሰውነት ውስጥ የሚፈጠሩትን ድምጾች ወደ ጆሮ በማስተላለፍ ለመስማት የሚረዳ መሳሪያ::

ማጅራት ገትር Meningitis

በባክቴርያ፣ በቫይረስ ወይም ሌሎች ጥቃቅን ዘአካላት በደም ስር በጉዳት ወይም ከአቅራቢያ ቦታዎች በመሰራጨት የአንገልና የሰረሰር መለከፍና መብገን:: በዚህ ጊዜ ትኩሳት፣ ብርሃን ለማየትና ድምፅ ለመስማት አለመፈለግ፣ መያዘት፣ አንገትን ሲያጥፉ ህመም መሰማት፣ መንፈራፈርና ነፍስን መሳት በየደረጃው ያስከትላል::

ማጋት Lactation

የጡት ወተት ማመንጨት ተግባር::

ማጋቻ ሆርሞን Lactogenic Hormone

ከፊተኛ አዕዩ እጢ የሚመነጭ ጡት ወተት እንዲያዘጋጅ የሚረዳ ሆርሞን::

ማጠፍ Fexion

የተዘረጋ አካልን ከአንጓ የማጠፍ ሁኔታ::

ማጥ /ፐማጥ/ Tenesmus

ያለፍላጎት ሰገራን ወይም ሽንትን ለማስወጣት የፊንጢጣ ወይም የፊኛ መጭጠሪያን መኮማተር የሚሰማ ህመም::

ማፀንአፍ Cervical

ወደ እምስ የሚከፈተው የማፀንገት ቀዳዳ::

ማፀንገት Cervix

የማህፀን አንገት እስከ ቦስት ሳንቲሜትር ርዝመት ሊኖረው የሚችልና አፋ ወደ ውጪ ሴት ብልት ክፍል የተከፈተ

ምላስርጢ Sublingual gland

ከምራቅ እጢዎች አነስተኛ የሆነና ከምላስ ስር የሚገኝ እጢ::

ምራን Ligament

ከጥረት ህብረህዋስ የተሰራ የአንጓ መገጣጠሚያን ለማያያዝና ከቦታው እንዳ ይናጋ የሚያደርግ::

ምርቀዝ Abscess

የመግል በጊታ ውስጥ መጠራቀም:: ከበሰለ በኋላ ራሱ ወደ ውጭ የሚፈርጥ ወይም በቀዶ ህክምና የሚበጣ::

ምርጊዝ Fibula

በባት በስተውጭ በኩል የሚገኝ ቀጭኑ ከጉልበት እስከ ቁርጭምጭሚት የሚደርስ አጥንት

ምትረተ ትርፍ አንጀት Appendectomy

በቀዶ ህክምና ትርፍ አንጀትን በመቁረጥ ከሰውነት ማስወገድ

ምትረት Ectomy

የአባላካል ወይም እጢ መቁረጥና ከሰውነት መለየት::

ምጡን Isotonic

የተመሳሰለ ስርገት ግፊት ወይም ውጥረት ያለው::

ምጥ Labour

ሽል ከማህፀን ውስጥ የሚወጣበት ድርጊት ሶስት ደረጃ ሲኖሩት አንደኛ ደረጃ ማህፀን ቁርጠት ከጀመረበት ማፀንገት ጠቀላላ እስከሚከፈትበት ሁለተኛ ደረጃ ማፀንገት ከተከፈተበት ሽሉ እስከወጣበት ሶስተኛ ደረጃ ሽሉ ከወጣበት እንግዴ ልጅ እስከሚወርድበት።

ምጥጥን ምግብ Balanced diet

ለሰውነት አስፈላጊ የሆኑትን ሙቀት ሰጪ ሰውነት ገንቢ ስቦችንና ቪታሚኖችን እንዲሁም ንጥረ ነገሮችን ያጠቃለለ ምግብ፣

ምጽጊት Phimosis

የሙርጥ ሽፋን /ቆለፌት/ መጥበብ ምክንያት የሽፋኑ ወደ እስኪት ዘንግ አለመቀልበስ።

## ረ

ሩቅ አዩታ Hypermetropia

የአይን ኳስ ቀርፀ በመዘጣቱ ወይም የብርሃን ስብረት መዛነፍ ምክንያት የብርሃን ጨረር ትኩታ ከአይን ኳስ ውጭ ሲሆን። ይህ በሽታ ያለው ሰው ቅርብ ነገሮችን ለማየት ሲያዳግተው ሩቅ ያሉትን ለማየት አይቸገረውም በመነፀር ይስተካከላል።

ራስ ልክፈት Auto infection

ልክፈትን ከአንድ የሰውነት ክፍል በጣቶች በፍጣ ወዘተ... ወደ አልተለከፈው ክፍል ማጋባት /ማዛመት/።

ራስ ቅል Carinum

አንገል የታቀፈበት፣ የአንጎል መከለያ ሳጥን መሰል አጥንት ክፍል።

ራስ ቅል Skull

ስምንት የአንጎል አጥንቶችና አስራ አራት የፊት አጥንቶችን የሚያጠቃልል።

ሬሳ ቤት Morgue

የሞተ ሰው ሬሳ ከመቀበሩ በፊት መቆያ ክፍል።

ርጋቢ ምላተልብ Diastole

የልብ ጡንቻ መኰማተሩን የሚያቆምበትና የልብ ርም ጋኖች በደም የሚሞሉበት /ወቅት/።

## ሰ

ሰ ሃደም Anemia

በመጠንም ሆነ በአይነት የቀይ ደም ህዋሳት በሰውነት ውስጥ ማነስ። ይህም በሚደርስበት ጊዜ ሰውነት ይገረጣል፣ በእንቅስቃሴ ጊዜ ትንፋሽ ያጥራል፣ ልብ በፍጥነት ይመታል፣ ድካም ይሰማል፣ እንዲሁም ራስን ያማል።

ሰበከት Donsum

የአካል በስተጀርባ በኩል።

ሰንበር Wheal

በአለንጋ እንደተመታ በቆዳ ላይ አገዶም ዝብ ብሎ የሚታይ።

ሰገራ Faeces

የተበላ ምግብ በአንጀት ተብላልቶ የሚቀረውና ከሆድ እቃ የሚወጣው ውዳቂ ውጤት፤ ያልተብላሉ ምግቦች፤ ባክቴሪያንና ውሃን ይይዛል።

ሰገራ Stool

ከአንጀት የሚወጣ ውዳቂ።

ሲቃ Dyspnea

በጤና መታወክ ወይም በሌላ ምክንያት ለመተንፈስ የሚያጋጥም ችግር።

ሲግማሰል ደንዳኔ Sigmoid colon

በግራ የታች ሆድ ክፍል በኩል በሚገኝ የሸለል አንጀት በላይ የሚገኝ የደንዳኔ ክፍል።

ሳልሞኔላ Salmonela

የባክቴሪያዎች ዝርያ የሆነና አጣዳፊ የአንጀት ብግነት የሚያመጣ።

ሳንባምች Pneumonia

በቫይረስ ባክቴሪያዎች ወዘተ... አማካይነት የሚደርስ የሳንባ ለከፌት።

ሴንቲግሬድ Centigrade

የሙቀት ልክ መስፈርት፤ በዚህ መስፈርት መሰረት የውሃ ነጥበ ፍሌት 100 /አንድ መቶ/ እርከን ሲሆን፤ ነጥበበረዶ ደግሞ 0 /ዜሮ/ እርከን ነው።

ሰለላት Atrophy

የሰውነት ህዋሳት ከአገልግሎት ውጭ በመሆን ወይም ምግብ በማጣታቸው ምክንያት መመንመን ምሳሌ፤ የጡንቻ መመንመን።

ሰለምታ Coma

በተለያዩ ምክንያቶች አእምሮን መሳትና የቀፀበ ታጤፊ ስሜት መጥፋት።

ስሜት አባላካል Sensory organ

የነርቭ ስሜቶችን ወደ አንጎል በማድረስ የተገኙ ስሜቶችን የሚሰጥ የሰውነት ክፍል። ምሳሌ፤ ጆሮ፤ ዓይን

ስምምነት Adaptation

ችግሮችን መቋቋምና ለመጪ ነገሮች ራስን ማዘጋጀት።

ሰረማእሰ Dermis

የደም ስሮችን ነርቮችን የወዝና የላብ እጢዎችን በያዙ ህብረ ህዋስ የተሰራው እውነተኛው ቆዳ ከላእላይ ማእሰ ስር ያለው።

ስር Vessel

በሰውነት ውስጥ ያሉትን ፈሳሾች የሚያስተላልፍ ቱቦ፤ ቦይ ወይም ካናል።

ስር ነቀ Nasopharynx

ከአፍንጫ ገታ በስተኋላ ከለሰላሳ ላንቃ ኋላ ያለው የትናጋ ክፍል።

ሰርጪት Infltration

በህዋስ በህብረህዋስና በአባላካል ውስጥ በመሰረግ ወይም መዝለቀ መከማቸት።

ስብ Fat

ነጭና ቀባትነት ያለው የእንስሳ ጮማ ህብረህዋስ።

ስብራት Fracture

በአጥንት ላይ የሚደርስ ስንጥቃት ወይም መለያየት።

ስ ነመ ነሻ Etiology

የበሽታ መነሻ ምክንያቶች የምናጠናበት ሳይንሳዊ ዘዴ።

ስ ነማአስ Dermatology

ስለ ቆዳ በሽታዎች የምናጠናበት የሳይንስ ክፍል።

ስ ነዐይን Ophtalmology

የአይን ሕክምና፣ ስለአይንና በሽታዎች የምናጠናበት የሳይንስ ክፍል።

ስ ነፅንስ Obstetrics

የፅንስ ህክምና፣ ሳይንሳዊ የሆነ የእርግዝና፣ የወሊድና የአርሳት እንክብካቤ ጥናት።

ስእርት Villus

በአንዳንድ ገለፈቶች ላይ የሚታይ አጭር ያለ ፀጉር መሳይ።

ስኳር ሽንት Glycosuria

በተለያዩ ምክንያቶች በሽንት ውስጥ ስኳር /ግሉኮስ/ መገኘት፣ የስኳር በሽታ አንደኛው ምልክት።

ስኳር በሽታ Diabetes mellitus

የመረጥ እጢ ኢንሱሊን ባለማምረቱ ስኳር ነት ያለውን ሽንት በብዛት የሚያሸና ውሃ ጥብ የሚያበረታና ከመጠን በላይ የሚያስርብና ምግብ የሚያስበላ በሽታ።

ስውር Occult

በአጉሊ መነፅር ወይም ኬሚካዊ ፈተና ብቻ መናረ የሚታወቅ፣ ገልፀ ያልሆነ፣ የተደበቀ፣ የተሸሸገ።

ስፌት Suture

የተለያዩ ወይም የተሰነጠቁ አካላት በቀዶ ህክምና ማገናኘት።

## ሸ

ሺስቶሶማ Schistosoma

የትላትሎች ዝርያ የሆነ ከተበከለ ውሃ የሰውን ቆዳ ሰርስሮ የሚገባና የአንጀትና የሽንት አባላካላትን የሚያጠቃ።

ሺገላ Shigella

ከቀላል ተቅማጥ እስከ ከባድና አጣዳፊ የሆነ ሽተቴ ተቅማጥ የሚያመጣ ባክቴሪያ።

ሻኝ Fundus

ገብ ብሎ የሚታይ ከመውጫ ቀዳዳ ራቅ ያለ የአባላካል ክፍል ምሳሌ ማህፀን ሻኝ፣ ወጋራ ሻኝ።

ሽል Fetus

ከሁለተኛ ወር እስከሚወለድበት ጊዜ ድረስ በማህፀን ውስጥ ለሚያድገው ፅንስ መጠሪያ።

ሽምቅና Intussuception

ከበላይ ያለ የአንጀት ክፍል ከበታች ባለው አንጀት ቦይ ውስጥ ተንሸራቶ መግባት።

ሽንተማጥ Dysuna

ሽንት ለመሽናት መቸገር ወይም ሽንት በሚሸናበት ጊዜ ህመም መሰማት።

ሽንት ጠፍ Anuna

ሽንት ከኩላሊት አለመፍለቅ።

ሽንት Urine

ከኩላሊት የሚመነጭና በፊኛ የሚጠራቀም እንዲሁም አብዛኛውን ጊዜ በፍላጎት በፊኛ ሽን ቱቦ የሚወጣ ፈሳሽ።

ሽንት ማነስ Oliguria

በተቅማጥ፣ ከፍተኛ መድማትና ማላብ የተነሳ የሽንት መጠን መቀነስ።

ሽንትውሃ Aminotic fluid

በማህፀን ውስጥ ሽሉን የሚከብ ፈሳሽ፣ እንሽርት።

ሽገት Mold

የበሰበሰ አትክልት ላይ የሚወጣ ዘረንጉዳይ።

ሽፋሽፍት Cilia

ሀ/ በአይን ቆብ ላይ ያለ ፀጉር ወይም ሽፋል ለ/ በአንዳንድ ህዋስ ላይ የሚገኝ ለመቀዘፊያ የሚያገለግል ረቂቅ ፀጉር'መሰል አካል።

ሽፍታ Rash

በአንዳንድ ተኩሳት በሚያመጡ በሽታዎች በቆዳ ላይ የሚወጣ ጊዜያዊ የቆዳ መንደብደብ።

## ቀ

ቀረባ Forceps

ነገሮችን ለማንሻ ወይም ለመቆንጠጥ የሚጠቀም የቀዶ ህክምና መሳሪያ ወረንጦ።

ቀሪብ Proximal

ለመሐል ወይም ለመነሻ ቀረብ ያለ፣ የሩቅ ተቃራኒ።

ቀሰቢት Bronchus

የቀሰብ መንትያ ከፋይ የሆነና ሳንባ ውስጥ በሚገባበት ጊዜ ራሱ ወደ አነስተኛ ቀርንጫፍ ቀሰቢቶች የሚከፋፈል የአየር መተላለፊያ ቱቦ።

ቀሰቢት አስም Bronchial asthma

በቀጭኑ ድምፅ እያሰማ የሚያስተነፍስ። በቀሰቢት ውስጥ ያሉ ጡንቻዎች በመኮማተር ወደ ውጭ ለመተንፈስ የሚያስቸግር። በሽታው በአንገገዳ ቀሳቀስት ወይም ውስጣዊ ስሜት ምክንያት ሊቀሰቀስ ይችላል።

ቀሰብ ከፍከዱ Epiglotis

ከለማፀም የተሰራና ምግብ በሚዋጥበት ጊዜ ወደ ቀሰብ እንዳይገባ የሚከላከል የማንቁርት መከደኛ።

ቀሳ Quarantine

ለከፈታዊ በሽታ እንዳይዛመት በሽታ የያዘውን ወይም የተጠረጠረን ሰው ለተወሰነ ጊዜ ማገለያ። ቀሳ ማውጫ

ቀስተገር አፅም Meta tarsal

የእግርን መሃል ከሚገነቡ አምስት ረዘምና ቀጠን ያሉ አጥንቶች አንዱ።

ቀንበጠ ጣእም Taste bud

የጣእምን ስሜት የሚያስተላልፍ በምላስ ላይ የሚገኝ የስሜት አባላካል::

ቀይ አራስፍስ Rubra

ከመውለድ በኋላ ለስድስት ቀናት ከማህፀን የሚፈስ ደም ያቀለመው ቀይ ፈሳሽ::

ቀይ ደም ሰሪት Hemopoiesis

የቀይ ደም ህዋስ አፈጣጠር ስርአት፣ ይህም የሚከናወነው በአጥንት መቅንና በጣፊያ ውስጥ ነው::

ቀዳማይ አንጀት Duodenum

ከጨጓራ እስከ ማእከላዊ አንጀት ያለው የመጀመሪያው 25 ሳንቲ ሜትር የቀጭን አንጀት ክፍል:: በዚህ ክፍል የጋራ የሃሞት ቦዩትና የመሬቅ ቦዩት ይከፈታሉ::

ቀዳማይ አንጎል Cerebrum

የአንጎል ትልቁ ክፍል የሆነና በራስ ቅል ውስጥ አብዛኛውን ቦታ የሚይዝ፣ ግራና ቀኝ ክፍል ያለውና የአንጎል ከፍተኛ ተግባር ማእከል::

ቀዳዳ Meatus

በሰውነት ላይ ክፍትነት ወይም ቱቦነት ያላቸው አባላካላት ክፍት መግቢያ ወይም መውጫ ምሳሌ የጆሮ፣ የፊኛ ሽን ወዘተ...

ቀዶ ህክምና Surgery

የህክምና አንዱ ክፍል የሆነና ሰውነትን በመክፈት ያልተስተካከሉ ወይም የተበላሹ የአካል ክፍልን ማስተካከል::

ቀለበት /የበለት/ Glans

ጀር መቀለ የወንድ ውጪ ዘርአባለ /ቁላ/ ወይም የቂንጥር እናት::

ቁምጥና ደረመን Leprosy

በማይከባክተርያ ሌፕሬ መነሻ የሚመጣ ተላላፊ የስጋ ደዌ በሽታ የአካልን እፅቅ የሚቆረጥ::

ቁርባ Anthrax

አጣዳፊ የሆነ ከቀንድ ከብቶች ወደ ሰው የሚተላለፍ ባሲለስ አንትራሲስ በተባለ ባክቴርያ የሚመጣ በሽታ፣ አባ ሰንጋ::

ቁርጠት Colic

ከኢተገዳጅ ጡንቻዎች የተሰሩ ቱቦዎች /ምሳሌ፣ አንጀት፣ ሃሞት ከረጢት/ በሚኮማተሩበት ጊዜ የሚሰማ ከፍተኛ ህመም::

ቁስል Wound

በአደጋም ሆነ በቀዶ ህክምና የህብረ ህዋስ መቆረጥ ወይም መለያየት::

ቁጣጥ Meconium

አዲስ የተወለደ ህፃን /ህገጠ/ በመጀመሪያ የሚወጣው ጠረን የሌለው ጠቆር ያለ ሰገራ::

ቁጥር Node

ዱቡልቡል የሆነ እትር ብሉ የሚገኝ አብጠት ወይም አባላካል ምሳሌ፣ ፍርንት አጤ::

ቁንጥር Ulcer

የቆዳ ወይም የገፍጥ ገለፈት በአደጋ በሙቀት ወይም በቀዝቃዛ በሚመዘምዙ ነገሮች ወዘተ... ምክንያቶች የሚደርስ መላጥና መጎድጎድ::

ቂንጥር Clitoris

በተገተር ታሪ ሀብረ ሀዋስ የተሰራና በሴት ብልት አናት ላይ የሚገኝ አፈጣጠ ሩ ከወንድ ብልት ጋር ተመሳሳይ የሆነ የሴት ብልት ክፍል።

ቂጥኝ Syphilis

ማንኛውንም የሰውነት ክፍል ደረጃ በደረጃ የሚያጠቃ ተላላፊ የአባለ ዘር በሽታ።

ቃር Heartburn

ሆምጣጣ የሆነ ነገር በመስቁ በሚተላለፍበት ጊዜ በደረት አካባቢ የሚያቃጥል ስሜት።

ቃጠሎ Burn

በፀሀይ ብርሃን፣ በሞቀ ፈሳሽ፣ በእሳት ወላፈንና ረመጥ፣ በኬሚካልና በኤሌትሪክ መነሻ በሰውነት ላይ የሚደርስ የመለብለብ ወይም የመከሰል ጉዳት።

ቄሳራዊ ማዋለድ Caesarian section

በልዩ ልዩ ምክንያቶች /ምሳሌ፣ የሽል ደንብ ወጥ አመጣጥ/ ሆድንና ማህፀንን በመቅደድ ሽሉን ማዋለድ።

ቀለመት Macule

ከአካባቢው ቆዳ ለየት ያለ ቀለም ያለው፣ ነገር ግን ዝብ ወይም ስርጉድ ያላለ የቆዳ ለውጥ፣ የተለያዩ ቀለም በፋትና ቅርፅ ሊኖረው ይችላል።

ቀምበ ውሃ Ascites

በሆድ እቃ ለበስ ጋታ ውስጥ የተጠራቀመ ፈሳሽ። በሆድ እቃ ለበስ መብገን፣ በደመላሽ ቱቦ መዘጋት ወይም በአጠቃላይ ውሃዘል ገላ ምክንያት በሆድ ውስጥ ጠሚጠራቀም ፈሳሽ።

ቅርፀብልሽነት Deformity

የሰውነት ቅርፅ በሙሉ ወይም በከፊል መበላሸት፣ መጣመም።

ቅርፊት Scab

በቁስል ላይ የሚጋገር የደረቀ እዥ።

ቅንባር System

በስራ በሚመሳሰሉ አባላካላትን በአንድ ላይ የሚያጠቃልል።

ቅንባር ልመት Digestive system

በአፍ የገባ ምግብ የሚተላለፍበት ቱቦዎችን /መስቁ ዉጋሬ ቀጭን አንጀት ደንዳኔ/ እንዲሁም ምግቡ እንዲልም የሚረዱ ፈሳሾችን የሚያመነዉ አባላካላትን /ጉበት፣ ሀሞት ከረጢት፣ መረጭ/ የሚያጠቃልል።

ቀዱሀት Paracentesis

የሰውነት ገታን በመርፌ በመውጋት ፈሳሽን ማውጣት።

ቀፍ ቀፋ Incubation

ከለከፈት ጊዜ ለበሽታው ከተጋለጡ በኋላ የመጀመሪያ ስሜት እስከሚሰማበት ወቅት ያለው ጊዜ።

ቀለጥ ብግነት Orchitis

በለከፈት ጉዳይ ወይም በጆሮ ደግፍ በሽታ ምክንያቶች የቀለጥ መብገንና ማበጥ።

ቆዳ Skin

ተከላካይ የሆነ ሰውነትን በስተውጭ የሚሸፍን።

## በ

**በላኢ ህዋስ** Trophozoite
ጥገኛ ካደረገው ህዋስ ምግቡን የሚያገኝና የሚያድግ ጥገኛ ህዋስ።

**በሽታ** Disease
የአእምሮ ወይም የሰውነት ጤንነት ማጣት፣ ህመም።

**በሽታ ስሜት** Symptom
በሰውነት ላይ በሚደርሱ ለውጦች የሚሰማ ያልተለመደ ስሜት።

**በናኝ** Volatile
በቀላሉ ወደ ትንነት ለመለወጥ የሚችል ፈሳሽ ወይም ጥጥር።

**በኩር** Preimigravida
ለመጀመሪያ ጊዜ ያረገዘች ሴት።

**ቡአ** Hernia
ውስጣዊ አባላካልን የሚያቅፍ ክርታስ ሲቀደድ ወይም ሲለወጥ ውስጣዊው አባላካል በተለወጠው ቦታ ወደ ውጭ መጎልጎል።

**ቢ.ሲ.ጂ** B.C.G
ሃይሉ ከተመናመነ የቲበርክል ባሲለስ የተዘጋጀ የሳንባ በሽታን ለመከላከል የሚሰጥ ክትባት።

**ቢጫ ወባ** Yellow fever
በክትባት ለመከላከል የሚቻል በወባ ትንኝ አማካኝነት የሚተላለፍና አጣዳፊ ልክፈት።

**ባህሪ አወራረስ** Heredity
አንዱን ህይወታዊ ከዘር ያው የሚወርደውን የተፈጥሮ መለያ ጠባይ ለመውረስ የሚያስችለው ሁኔታ ምሳሌ፣ የሰውነት ግዝፈትና ቅርፅ፣ የፀጉርና የቆዳ ቀለም፣ ለበሽታዎች መጋለጥ ወዘተ.

**ባምቡሌ** L.G.V (Lymphogranuloma Venerium)
በቫይረስ አማካይነት በግብረስጋ ግንኙነት የሚመጣ የአባለዘር በሽታ። በብልት ላይ ትንሽ ቁስልና የብሽሽት እባጭ ይኖራል።

**ባሲለስ** Bacillus
ዘንግ መሰል ባክቴሪያ።

**ባሲላዊ ተቅማጥ** Bacillary dysentery
በባሲለስ መነሻነት የሚመጣ ደም የሚያስቀምጥ የአንጀት በተለይ የደንዳኔ ልክፈት።

**ባክቴሪያ** Bacteria
በአይን የማይታዩ እጅግ ጥቃቅን የሆኑ በአመቺ ሁኔታዎች በመከፋፈል የሚባዙ ባለ አንድ ህዋስ ህያው ተሃዋስያን። ብዙዎቹ ባክቴሪያዎች በሰውነት ውስጥ በሚባዙበት ጊዜ ህብረ ህዋስን በማፈራረስ ወይም መርዞችን በመስራትና በደም ውስጥ በማሰራጨት ልክፈትን ያስከትላሉ።

**ብራኳ** Scapula
ጠፍጣፋና ሰፊ የሆነ ሶስት ማእዘን ቅርፅ ያለው ከትከሻ በስተኋላ የሚገኝ አጥንት።

ብሽሽት Inguinal
የሆድና የጭን መገናኛ የላሉ ማጠፊያ ቦታ።

ብብታዊ ሙቀት Axillary temprature
የሰውነትን ሙቀት ለመለካት ቴርሞሜትርን በብብት ውስጥ ማስቀመጥና የሚገኘው የሙቀት አርከን።

ብብታዊ ደምሥር Axillary artery
በብብት ውስጥ ያለው ዋነኛው ደምሥር ቱቦ።

ብብት Axilla
ወርቾና ጎንዩ ደረት የሚገናኙበት ጎድጓዳ የሰውነት ክፍል።

ብክለ Contamination
ንፁህ የሆነን ቦታ በመነካካት ጥቃቅን ህዋሳትን በመበከል ተውሳክን ማዛመት።

ብግነ Cellulitis
በስተሬፕቶከክ ባክቴርያ ልክፈት መነሾ የሁበር ህዋስ መብገንና የተለከፈው ቦታ አብጦት። ምርቀዝ ግን አይፈጥርም።

ብጉር Acne
በቆዳ ላይ ያለው እጢ እጬ ብግነት በሚደርስበት ጊዜ በፊት በአንገትና በደረት ላይ የሚወጣ እብጠት /እትራት/።

ብግነት Inflammation
ከኬሚካዊ ሜካኒካዊ ባክቴርያዎና መርዛዊ ጉዳቶች በኋላ በህብረህዋስ ላይ የሚታይ አጸፋ ምልክት፤ ጉዳት የደረሰበት ቦታ የተዋረደ ለውጥ ካደረገ በኋላ በአካባቢ ሕዋሳት ጥገና ይደረግበታል፤ ዋና ምልክቶቹ ህመም /ስቃይ/ ሙቀት ቀላትና እብጠት ናቸው።

ብጣት Incision
ለቀዶ ህክምና አላማ ሰውነትን በስለት መቁረጥ ወይም መሰንጠቅ።

ቦዩት Duct
ከእጢዎች የመነጨ ፈሳሽ የሚያልፍበት ቱቦ ወይም ቦይ። መንጨረር።

ቧንቢት Fistula
ደንብወጥ የሆነ መተላለፊያ ቱቦ፤ የአንዱን አባላካል ገጽ ከሌላው የሚያ ገናኝ ወይም አንዱን ገጽ ከቆዳ ውጭ /ሰሌዳ/ የሚያገናኝ።

ተ

ተላላፊ Contagious
ከአንድ ሰው ወደ ሌላው የሚተላለፍ በሽታ።

ተላላፊ በሽታ Communicable disease
ከአንድ ሰው ወደ ሌላ ሰው የሚተላለፍ በሽታ። ተጋቦት በሽታ

ተራዓ Axis
ሁለተኛው የአንገት አከርካሪ አጥንት።

ተቀባይ Host
ጥገኛ ዘአካል ምግቡን በማግኘት የሚኖርበት ህይወት ያለው አካል።

ተቅማጥ Diarrhea

በባክቴርያ ለከፍተ፣ በመርገት ወይም በስሜታዊ ምክንያቶች ቀጠን ያለን ሰገራ በብዛትና በተደጋጋሚ መውጣት።

ተን ተልሽ Occiput

የራስ ቅል ኋላኛው ክፍል።

ተወጋጅ Waste

ለሀይወት ጠቃሚ ያልሆነ ከሰውነት የሚወጣ ውዳቂ ወይም ቆሻሻ።

ታህታይ ዋና ደመላሽ Inferior Vena Cava

ከታችኛው ክፍለአካል ደመላሽ ቱቦዎች ደምን በማሰባሰብ ወደ ልብ የሚያስገባው ዋናው የደም ቱቦ።

ቴርሞሜትር Thermometer

የሙቀትን ወይም ብርድትን መጠን ለመለኪያ የሚያገለግል መሳሪያ።

ትል Worm

ርዝመት ያለውና አከርካሪ የሌለው እንስሳ ምሳሌ፣ ወስፋት፣ ኮሶ ትል።

ትልቅ አንጀት Large Intestine

ከኋዓንጀት እስከ ፊንጢጣ ድረስ ያለው የአንጀት ክፍል ደንዳኑ።

ትርጋጽ Distal

ከሰውነት መሃል ነጥብ የራቀ ወይም ከመነሻው ነጥብ የራቀ ክፍል።

ትርፍ አንጀት Appendix

ከኋዓ አንጀት የተጣበቀና ትል መልክ ያለው ቱቦ የአንጀት ክፍል። ከሰባት እስከ አስራ አምስት ሳንቲ ሜትር ርዝመት ሊኖረው ይችላል።

ትርፍ አንጀት ብግነት Appendicitis

የትርፍ አንጀት ብግነት።

ትናጋብጠት Adenoid

በእንጥልና ቶንሰል አካባቢ የፍርንት እጢ ደንበወጥ እብጠት።

ትንታ Aspiration

ከአፍ፣ ከሰርን ኋታ ውስጥ ፈሳሽ ወይም ጠጥሬ ነገሮች ወደ ቀሰብና ሳንባ መግባት።

ትከሻ ጡንቻ Deltoid muscle

ትከሻና ላይ ክንድ መጋጠሚያ ላይ የሚገኝ ሶስት ማእዘን ቅርፅ ያለው ጡንቻ የክንድ መርፌ የሚወጋበት ጡንቻ።

ትኩሳት Fever

የሰውነት ሙቀት ከመጠን በላይ መጨመር፣ ትርታና ትንፈሳ የሚጨምር፣ ቆዳ የሚያዳርስ፣ ጥቂትና የወየበ ሽንት የሚያሸና፣ ማስታወክና ራስ ምታት የሚያስከትል።

ትክትክ Whooping cough

በህፃናት ላይ የሚደርስ የመተንፈሻ ቧንቧዎች ልክፈት አከታትሎ የሚያስልና በሳሉ መጨረሻ ላይ የተለየ ድምፅ የሚሰጥ።

ትውከት Vomit

በጨጓራ ውስጥ የነበረ በአፍ ተመልሶ የሚመጣ።

ቸ

ቸፍርግ Glomerulus

በቦውማ ከረጢት የተከበበ ፀጉር ደም ስሮች ስብስብ፤ ደምብ በማጣራት ሽንትን የሚያመ ነው።

ነ

ነርቫዊ ቅንብር Nervous system

በጣም ውስብስብና ረቂቅ የሆነ እርስበርሱ ግንኙነት ያለው የነርቭ ህብረህዋስ ክምችት፤ አንጎልን፤ ሰረሰርንና የነርቭ ስሮችን የሚያጠቃልል።

ነቀርሳ Tuberclosis

በቶበርክሎ ባሲለስ አማካኝነት የሚመጣ በተለይ በመተንፈሻ ቅንብር ላይ የሚደርስ በሽታ ሌሎች የሰውነት ክፍሎችም በበሽታው ሊጠቁ ይችላሉ።

ነገርጋር Epilepsy

ነፍስን በማሳት የሚጥልና ሰውነትን የሚያወራጭና የሚያንፈራግጥ የአንጎል በሽታ። የሚጥል በሽታ።

ናሙና Specimen

የአካልን አጠቃላይ አይነትና ሁኔታ ለማየት /ለመመርመር/ የሚወሰድ ክፍል።

ንቃት አእምሮ Consciousness

በአእምሮ ነቅቶ በአካባቢ ያሉትን ሁኔታዎች ለመረዳትና ለመለየት መቻል።

ንድፍት መርዝ Venom

በአንዳንድ እንስሳት /እባብ፤ ተባይ/ እየተዘጋጀ በንድፈት ወይም ውጊት ወደ ሰውነት የሚገባ መርዝ።

ንፋጭ Mucous

ከንፋጭ ገላፈትና ከእጢዎች የሚመነጭ መጣበቅነት ያለው ለድላቹ ፈሳሽ፤ እንደ ንፍጥ ያለ ነገር።

ንፋጭ ገለፈት Mucous membrane

ንፋጭ አመንጭ ህዋስ ወይም እጢ ያለው በሰውነት ውስጥ ያሉ የአንዳንድ መተላለፊያዎችና ገታዎች የሚሸፍን ገበር።

ንፍርቅ እባጭ Caruncle

በአንድ አካባቢ በርከት ብሎ ከቆዳ ስር እንደምርቅዝ እባጭ እየፈነዳ የሚወጣ ቁስል።

ንፍቅ ደረት Mediastinum

ከእምቢያና የደረት አከርካሪ መሃል የደረት አባላካላትን /ልብ፤ ትላልቅ ደም ስሮች፤ መስቴ ወዘተ.../ የያዘ ከሁለቱ ሳንባዎች መሃከል የሚገኝ ክፍለአካል።

አለመቋጠር Incontinence

በአንጎል ወይም ሰረሰር መታወክ በፊኛ ወይም በፊንጢጣ መቋጠሪያ መላላት ሽንትን ወይም ሰገራን ለመቋጠር አለመቻልና ማንጠባጠብ::

አለርጂ Allergy

ለሰውነት አንግዳ የሆኑ ነገሮችን በትንሽ መጠን በሚገቡበት ጊዜ ብርቱና ኃይለኛ ቁጡ መታወክ በበሽተኛው በሚደርስበት ጊዜ ምሳሌ፣ አስም::

አልካሊ Alicali

ከአሲድ ጋር ሲዋሃድ ጨውን፣ ከስብ ጋር ሲዋሃድ ሳሙናን የሚፈጥር ልዩ ቁስ:: ቀይ ሊትሙስን ወደ ሰማያዊ የሚቀይር፣ በህክምና ሶድየም ፖታሲየምና አሞንያ ዋና ዋናዎቹ ናቸው::

አሜባ Amoeba

ከፕሮቶዞአ ባለ አንድ ህዋስ ቤተሰብ የሆኑ፣ ከነዚህም አንዱ አይነት /ኢንታሜባ ሂስቶሊቲካ: ተቅማጥን የሚያመጣ ህዋስ::

አሜባ በሽታ Amoebiasis

በኢንታሜባ ሂስቶሊቲካ መለከፍ ምክንያት የደንዳኔ መቁሰል፣ እንዲሁም በጉበት ውስጥ የአሜባ ምርቅዝ መፈጠር::

አሜባ ተቅማጥ Amoebic dysentery

በኢንታሜባ ሂስቶሊቲካ በመለከፍ የሚመጣ ተቅማጥ::

አምባር Wrist

እጅና ክንድ የሚገናኙበት መገጣጠሚያ ቦታ::

አራስፍስ Lochia

ደም፣ ንፋጭና ህብረህዋሶች የያዘ በአራስነት ጊዜ ከማህፀንና ብልት የሚወጣ ፈሳሽ:: በመጀመሪያ ደም የበዛው ቀጥሎ ቡናይነት መልክ ያለው ከዚያም ነጭ ፈሳሽ ይሆናል::

አራጊ ልክፈት Ascending infection

ከታች ክፍለ አካል ወደላይኛው የሚዛመት ልክፈት ምሳሌ፣ ከፊኛ ወደ ኩላሊት የልክፈት መዛመት::

አሲዳዊ Acidic

አሲድነት ያለው ልዩ ቁስ::

አሲድ Acid

ከአልካሊ ጋር ሲደባለቅ ጨውን የሚፈጥር፣ ማንኛውም ልዩ ቁስ ሰማያዊ ሊትመስን ወደ ቀይ የሚቀይር::

አስም Asthma

ብርቱና ድንገተኛ የሆነ የትንፋሽ ማጠር::

አስታላፊ ተቀባይ Intermediate Host

ጥገኛ ህዋስ በእጭነቱ ጊዜ የሚያልፍበት ደንደስ የለሽ እንስሳ ምሳሌ፣ ለወባ በሽታ የወባ ትንኝ ነው::

አሻቃቢ ደንዳኔ Ascending colon

ከጊዳ አንጀት በመነሳት ጉበትን መታጠፊያ ድረስ ያለውና በስተቀኝ የሆድ ጎታ በኩል ያለው የደንዳኔ ክፍል::

አቢይ ደምሥር Aorta

ከግራ ከርስ ልብ የሚነሳ ትልቁ የሰውነት ደምሥር ቱቦ:: ሆዳዊ አቢይ ደምሥር በሆድ ውስጥ ያለው ክፍል አቢይ ደምሥር ቀስት፤ ከልብ ሲነሳ ያለው ቆልማማ ክፍል:: ደረታዊ አቢይ ደምሥር በደረት ውስጥ ያለው ክፍል::

አባለዘር በሽታ Venerial disease

በሽታው ካለበት ሰው ጋር በግብረ ስጋ ግንኙነት የሚመጣ ተላላፊ በሽታ::

አብሮለድ Congenital

ከመውለድ በፊት ወይም በልደት ጊዜ ለሚኖሩ ሁኔታዎች የተሰጠ ስም ምሳሌ፤ ወርዔነት::

አትኳሽ Febrile

ትኩሳትነት ያለው፤ ትኩሳት በሰውነት ላይ የሚያመጣ::

አትላስ Atlas

የመጀመሪያው የአንገት አከርካሪ:: ራስ ቅልን የተሸከመው የመጀመሪያው ደንደስ::

አኔሳ Sacrum

የዳሌ ገንዳ /ቂሬ/ የኋላ ክፍል የሆነና በአምስት የተጣበቁ የአከርካሪ አጥንቶች የተሰራ ሶስት ማእዘን አጥንት::

አናት Apex

ቀምበብ አጓም ያለው ነገር ሁሉ ሹሉ ወይም ጫፍ ክፍል::

አናቶሚ Anatomy

ስለ ሰውነት ክፍሎች የምናጠናበት ሳይንስ::

አንጀት ተስቦ /የ/ Typhoid

አጣዳፊ የሆነና ትኩሳት፤ ራስ ምታትና የሆድ ሁከት የሚያመጣ በሳልሞኔላ ባክቴሪያ መነሻ የሚደርስ ተላላፊ በሽታ::

አንጀት አገዳት Intestinal obstruction

በተለያዩ ምክንያቶች የአንጀት ቦዩ መዘጋት ይህም በሚደርስበት ጊዜ ቁርጠት ማስታወክ ሰገራ ድርቀት ሆድ መነፋትና ሽብጠት ወዘተ ይኖራል::

አንጎል Brain

በራስ ቅል ውስጥ የሚገኘው የማእከላዊ ነርቭ ቀንበር ክፍል:: ይህ ነጭና ለስላሳ የሆነ ህብረ ህዋስ የአእምሮ ማስተዋል ችሎታ የመማር ወይም የመረዳ ትና ችሎታ ያለው የእውቀት ማእከል::

አንጎል ሽብረት Concussion

በሃይለኛ ምት ምክንያት በአንጎል ላ~ የሚደርስ ሁከት:: በዚህም ምክንያት ህይወትን መሳት::

አንጓ Joint

ሁለት አጥንቶች የሚገናኙበት መገናኛዎች የማይንቀሳቀሱ /ምሳሌ አፀመአንገር/ በመጠኑ የሚንቀሳቀሱ ሊሆኑ ይችላሉ::

አንፈከርስ ቱቦ Nasogastric tube

ምግብ በአፍ ለመውሰድ የተሳነው ሰውን ለመመገብና በጨጓራ ውስጥ ያለን ነገር ለማውጣት የሚጠቀም በአፍንጫ በኩል ወደ ጨጓራ የሚገባ ረዝም ያለ የፕላስቲክ ቱቦ::

አካ በሽታ Endemic

·በአንድ የተወሰነ አካባቢ ተስፋፍቶ የሚገኝ በሽታ።

አካፋይ Septum

ገበሬታዊ የሆኑ ሁለት ንታያችን የሚከፍል /የሚለያይ/

አክታ Sputum

በመሳል ወይም ጉሮሮን በመጥረግ የሚወጣ ፈሳሽ፤ በውስጡ ህዋሳትን ለጋንን ደም ወይም መግል ሊይዝ ይችላል።

አውታፍ Embolus

በደም ዝረት ውስጥ በመጓዝ ጠበብ ባለ ደም ስር ሲደርስ የሚዘጋ እንደረጋ ደም፤ አየር አረፋ ብትንትን ህብረህዋስ ወዘተ... ያለ ነገር ሁሉ።

አውደፀአት Perineum

ከፊንጢጣና ከብልት መሃከል ያለው አካባቢ።

አዝጋሚ የልብ ምት Brady candia

ደንብ ወጥ የሆነ ዝቅተኛ የልብ ምት ወይም ትርታ ፍጥነት።

አይነርገብ Retina

በነርቭ ሕብረህዋስ የተቀናጀ ምስል የሚያርፍበት የአይን ሉል የውስጥ ልባስ።

አይን Eye

ሶስት ልባስ ያለው ድቡልቡል ያለ የሉል ቅርፅ ያለው የማያ አባላካል።

አይን ማዝ Trachoma

ተላላፊ በሆነ ቫይረስ በአይን ሽፋን ላይ የሚደርስ ለከፈት፤ የድርግታይን እብጠት ብሎም ዝብር መፍጠር ከዚያም ጠባሳ በአይንና በአይን ቆብ ላይ የሚፈጥር።

አድሬኖኮር ቲክ ትሮፊክ ሆርሞን Adrenocortico trophic hormone

ከፊተኛ አዋይ እጢ ገርባብ የሚመነጭና የኩላሊት እጢ አናት ኮርቲን ሆርሞንን እንዲያመነጭ የሚያደርግ ሆርሞን።

አገልባች Booster

ውጤት እንዲጨምርና እንዲቀጥል የሚረዳ። ቀደም ብሎ የተሰጠ ክትባት ሃይሉ እንዳይቀዘቅዝ በድጋሚ የሚሰጥ ክትባት።

አጣዳፊ Active

በድንገት ደርሶ በአጭር ጊዜ ውስጥ ከባድ የህመም ስሜትን የሚያመጣ ስር ያልሰደደ ወቅት የማይሰጥ ህመም።

አጥንት ብግነት Osteomyelitis

በጉዳት ወይም ልክፈት የመቅን ወይም የአጥንትና መቅን መብገን።

አፀመ መዳፍ Metacarpal

የእጅን መዳፍ ከሚገነቡ አምስት ረዘም ያሉት አጥንቶች አንዱ።

አፀመ አንባር Carpal

አምባርን አምባር መዋያን የሚፈጥሩ በሁለት ረድፍ የሚገኙ ስምንት አጥንቶች ስብስብ መጠሪያ።

አፅመ ክሳድ Claville

በፊለፊት በኩል በትከሻና አንገት መሃል የሚገኝ ቀለማማ አጥንት። ብሬ ወይም ማጧአጥንት /ማጭድ አጥንት/።

አፍአመርዝ Exotoxin

ጥቀን አካላት ወይም ባክቴርያ ወደአካባቢያቸው የሚረጩት መርዝ።

ኡደተ ደም ቀንባር Circulatory system

ደም በሰውነት ውስጥ የሚዘዋወርበት ስርአት። ደም ከልብ በመረጩት ወደ አቢይ ደምባዙና ቀርንጫፍ ደምባዞች በመጨረሻም ወደ ፀጉር ደም ስሮች በመ ፍሰስ ከዚያም በደም መላሽ ደም ስሮች አማካይነት ወደ ልብ የሚመለስበት ስረአተ ኡደት።

ኢሸርሸታ Indigestion

የተበላ ምግብ በጨጓራና ቀጣይ ቀጭን አንጀት በደንብ ባለመብላላቱ የሚደርስ ማቅለሽለሽና ማስታወክ፣ ማጃርና አሲድ መለበቅ፣ የጋዝ መጠራቀምና ማገሳት ወዘተ.

ኢፈቂደምግብ Anorexia

በበሽታ ወይም በጭንቀትና በገለፍተኝነት ምክንያት ምግብ አለመብላትና የሰውነት መመንመን።

ኤሌክትሮላይት Electrocyte

የኮረንቲያዊ ፍርሰት ተቀረዶ ለውጥ የሚደርስበት ልዩ ቅስ።

ኢስትሮጀን Estrogen

የሴቶ ጾታን የሚወስን ከእንቁልአል የሚመነጭ ሆርሞን።

ኢክላምፕሲያ Eclampsia

በእርግዝና ጊዜ የሚደርስ አንቀጥቀጥ ወይም አንፈርፋሪ በሽታ። ይህ በሽታ ሲደርስ የደም ግፊት መጠን መጨመር፣ የሰውነት ክብደት መጨመርና በሽንት ውስጥ የፕሮቲን መገኘት ምልክቶች ናቸው።

እሙከ Vernix caseosa

ከሽል ቆዳ እጢዎች በመመንጨት ሽሉ ሲወለድ ገላው ላይ የሚለደፍ ቀራ መሳይ ነገር።

አማሬ Demonstration

ጉዳዮችን በመገለጫዎች አማካይነት ማስረዳት።

አምሳፍ Vulva

ከጭገር ፊት በታች ያለ የሴት ብልት የውጭ ክፍል።

እምስ Vagina

ከምሳፍ ወደ ማፀንንት የሚያስተላልፍ የሴት ገብረስጋ መገናኛ ቱቦ።

አምቢያ Sternum

ጠባብና ጠፍጣፋ የሆነ በደረት ፊት ለፊት የሚገኝ አጥንት።

አርሳት ጊዜ Puerperium

ከመውለድ በኋላ ለስድስት ሳምንታት ማህፀን ወደ ቀደመ እርግዝና ሁኔታው የሚመለስበት ጊዜ።

**አርግቢግቢት** Fontanelle

በሽልና ህፃናት የራስ ቅል አጥንቶች መሃከል የሚገኝ ብሩና ቀዳዳ አርግብ ግቢት በቀርን ራስ ቅልና ከግንባር ራስ ቅል መሃከል የሚገኘውና በአንድ አመት ዙሁል አደጫ የሚገጥመው፣ ድሃራይ አርግብግቢት የተገተለሸ ራስ ቅልና ከቀርን ራስ ቅል መሃከል የሚገኘውና በውለደት ጊዜ የሚገጥመው::

**አስተንፋስለባ** Apnea

በደም ውስጥ የከርቦንዳይኦክሳይድ እጥረት ምክንያት የሚደርስ ጊዜያዊ የመተንፈስ መቆም::

**አስኬት** Penis

የወንድ ገብረሥጋ መገናኛ አባላከል፣ የወንድ ጠፍረተሥጋ፣ ቁላ::

**አስኬት ጆር** Epididymis

ተምዘምዘ ቱቦ ክምችት የሆነ የአስኬት በስተኋላ ተባብቆ የሚገኝ ቀለል ያለ ቅርፅ ያለው የአስኬት ተቀያ፣ ከአስኬት የሚወጣው ዘር ፍስ በዚህ አካል ወደ ቱቦ አስኬት ይተላለፋል::

**አተሬ** Papule

ጠጠር ያለና በቆዳ ላይ ጉብ ብሎ የሚወጣ አነስተኛ እብጠት::

**እንቁላል** Ovum

የሴት አርባታ ሕዋስ ከበሰለ የግራፍ ጉብር የሚወጣ ከወንዱ ዘር ጋር ከተገናኘ በኋላ ዘር ያውን -የያዘ ፍጥረት ሆኖ ያድጋል::

**እንቁልጣል** Ovulation

በወር አበባ ኡደት በአስራ አራተኛው ቀን ከበሰለ የግርፍ ጉብር የእንቁላል መውጣት::

**እንቅልፍጠት** Insomnia

በአእምሮ ድካም በሀሳብ በስጭት በተለይ እንቅልፍ አይወስደኝም ብሎ በማሰብ እንቅልፍ ማጣት ወይም ሸለብ እያደረገ እንደገና መንቃት::

**እንቅር ቲት እጢ** Parathyroid Gland

ከእንቅርት እጢ በስተኋላ ተለጥፈው ወይም ተቀብረው ከሚገኙ ውስጥ አመንጭ እጢያች አንዱ በደም ውስጥ የካልሲየምና የፎስፈረስን ሚዛን የሚጠብቅ::

**እንቅርት እብጠት** Goitre

በአዮዲን እጥረት፣ በብግነት ወይም ለከረት፣ በጩና እብጠት፣ የእንቅርት እጢ የናረ ወይም ዝቅተኛ የተግባር ምክንያት የሚደርስ የእንቅርት እጢ መጠን መጨመር::

**እንቅርት /እጢ/** Thyroid gland

ውስጠ አመንጪ የሆነ በአንገት ፊት ለፊት ለቀስበና ማንቁርት ላይ ተለጥፎ የሚገኝ እጢ::

**እንክብል** Tablet

አነስ ብሎ ጠፍጠፍ ያለ መድሃኒትነት ያለው::

**እንዚራ** Vocal cord

በማንቁርት ውስጥ የሚገኝና ድምፅ ለመስጠት ወይም ለመፍጠር የሚርገበገብ የሚነዝር

አንገር Colostrum

ከወሊድ በኋላ ከእናት ጡት የሚወጣው የመጀመሪያው ወተት። አንገር በፕሮቲን ይዘቱ ከወተት ይበልጣል።

አንጋለለ Supine

ፊትን ወደላይ አድርጎ በጀርባ መተኛት።

አንጋለብጥ Lithotomy

ጉልበቶች ተንፈራክ በጀርባ ተኝቶ ጭንን በሆድ ላይ፣ ባትን በጭን ላይ በማጠፍ ለማህፀን ምርመራ ወዘተ... በሚያመች ሁኔታ መተኛት።

አንግዳ አካል Antigen

ለሰውነት እንግዳ የሆነ ልዩ ቁስ፣ ባክቴርያም ሆነ ሌላ በአድ አካል ሰውነት ውስጥ በገባ ጊዜ ፀረ እንግዳ አካል እንዲፈጠር የሚያደርግ።

አንግዴ እብጠት Tumor

ጥቅም የማይሰጥ አንዳንዴ የሚጎዳ ህገ ወጢ የሆነ በሰውነት ላይ ወይም ውስጥ የሚገኝ አዲስ እብጠት።

አንግዳ አፍነት Orthopnea

በከባድ የልብ ድካም ውሃዘል ሳንባ ቁሰቢትና ልብ አስም ወዘተ... ምክንያቶች ለመተንፈስ መቸገር በመቀመጥ በመቆም ወይም ትራስን ከፍ አድርጎ በመተኛት የሚሻል ትንፋሽ እጥረት።

አንፍርፍሪት Seizure

ድንገት የሚመጣ ስቃይ ወይም የሰውነት መንቀጥቀጥና መንፈራፈር።

እከክ Scabies

ከእከክ ተባይ ቆዳ ውስጥ ቦርቡሮ በመግባት የሚመጣ ተላላፊ የሆነ የሚያሳክክ የቆዳ በሽታ፣ በተለይ እጅና እግር ጣቶች መካከል በብብትና ብሽሽት አካባቢ የሚወጣ።

እዠህ Exudate

በገታ የተጠራቀመ ፈሳሽ እንደመግል ወይ እዥ ያለ።

እዠት Effusion

የደም ወይም የእዥ በአካባቢ ህብረህዋሳትና ገታ ውስጥ መጠራቀም።

እዥ ቋጠር Blister

በልዩ ልዩ ምክንያት በላይ ቆዳ ስር የእዥ መጠራቀም።

እጅ Hand

ከክንድ ጋርአምባር አንጓ ላይ የሚገናኝ ስምንት አፅመአንባሮች፣ አምስት አፅመዳፍቾችና አስራ አራት የጣት አጥንቶች ያጠቃለለ የሰውነት ክፍል።

አገዳ Obstruction

አንድ አካል መተላለፊያ በደንብ እንዳይሰራ መዘጋት።

እጢ Gland

በተለያዩ የሰውነት ክፍሎች የተለያየ ዓይነትና ተግባር ያለው አመንጪ አባላካል።

እጥበት Irrigation

ቦይነት ጠባይ ያላቸውን የሰውነት ክፍሎች የጆሮ አንጀት ፊና ፈሳሽ እየረጩ ማጠብ ወይም ቁስለን በፈሳሽ ማጠብ።

እጥናት Fumigation

አካባቢን በበናኝ ጢስ ወይም ጋዝ በማጠን ጀርሞችን ወይም ተባዮችን ማጥፋት።

እጭ Larva

ከእንቁላል ከተፈለፈለ በኋላ ነገር ግን ሙሽሬ ሳይሆን ያለው የተባይ እድገት ደረጃ።

ኦክስጂን እጦታ Anoxia

በህብረ ህዋስ ወይም አባል አካል ውስጥ የኦክስጂን እጥረት ምሳሌ፣ የአንጎል ኦክስጂን እጦት፣ በቂ የሆነ ኦክስጂን በአንጎል ውስጥ አለመገኘት።

## ከ

ከረጢት Sac

እንደቦርሳ ያለ ፈሳሽን፣ አየርን ወይም ሌሎችን ጠቅሎ የሚይዝ።

ከርክር Chancroid

የአባለዘር በሽታ፣ በብልት ላይ በዱክሬ ባሲለስ ምክንያት የሚወጣና የሚያም ቁስል ወይም አርምዱ።

ከንተር Tibia

ወደ ውስጥ ጠለቅ ያለው ከጉልበት እስከ ቁርጭምጭሚት መካከል የሚገኝ አጥንት።

ከፍተኛ የቅሬት ትውከት Hyperemesis Gravidarum

በእርግዝና ጊዜ የሚመጣ ከፍተኛ ተከታታይ ትውከት።

ከፍተኛ የደም ስኳር Hyperglycomia

በደም ውስጥ የስኳር /ግሉኮስ/ መጠን መብዛት፣ ምሳሌ፣ ስኳር በሽታ በዚህም ምክንያት ሽንት ይበዛል፣ ውሃም ይጠማል።

ከፍተኛ የደም ግፊት Hypertension

በደም ስሮች ጥበት ምክንያት በሚነሳ የደም መተላለፍ እገዳ፣ ለአንድ ሰው ለእድሜው ከተወሰነው በላይ የደም ግፊት ሲኖር፣ የልብ ድካምን፣ አንጎል ውስጥ ደም መፍሰስን ወዘተ. የሚያስከትል።

ኩሊትገ እጢ Adrenal gland

በኩላሊት አናት ላይ የሚገኝ፣ ውስጠ አመንጭ እጢ።

ኩላሊት Kidney

አደንጓሬ ቅርፅ ያለው፣ ከሆድ ገታ በስተኋላ በአከርካሪ አምዱ ጎን ያለ ተወጋጅ ውጤቶችን በሽንት መልክ የሚያስወግዱ አባላካል።

ኩላሊት ጠጠር Kidney stone

በኩላሊት ጧባ ውስጥ ጠጠር መገኘት ወይም መፈጠር።

ኩፍኝ Measels

በክትባት ለመከላከል የሚቻል በቫይረስ አማካይነት የሚመጣ ተላላፊ በሽታ እንደ ጉንፋን ጀምር በቆዳ ላይ የራሱ ጠባይ ያለው መፈንዳዳት የሚያሳይ፣ አብዛኛውን ጊዜ ከጕልምስና በፊት የሚወጣ፣ ከስድስት ወር እድሜ በፊት ግን የማይወጣ፣ አንዴ ከወጣ ተመልሶ የማይደገም።

ኬሞፈውስ Chemotherapy

ኬሚካል ውሁድ የሆኑ መድሃኒቶችን በመጠቀም በሽታዎችን ማከም።

ኪንታርት Wart

በቫይረስ አማካኝነት በቆዳ ላይ ጉብ ብሎ የሚወጣ።

ካርቲድ ደምሳጅ Carotid Artery

በአንገት ውስጥ ያለው ወደ አንጎል ደም የሚወስደው ዋናው የደም ቱቦ።

ካቴቴር Catheter

ከሰውነት ገታ ወይም ሰመት ፈሳሽን ለማውጣት የሚጠቀም ውስጠ ክፍት ከላስ ቲክ ወይም ከብረት የተሰራ ቱቦ።

ካንሰር Cancer

መነሻው በትክክል እስከዛሬ ያልታወቀ በልዩ ልዩ የአካል ክፍሎች ደንበወየ በሆነ አስተዳደር በአካባቢው በመስፋፋትና በደም ስሮች በመሰራጨት ለሞት የሚያደርስ ቁመና /የነቀርሳ/ በሽታ።

ክሊኒክ Clinic

ሕሙማን በተመላላሽ ደረጃ የሚመረመሩበትና የሚታከሙበት በገጠርም ሆነ በከተማ የሚገኝ የጤና ተቋም።

ክርናጥንት Ulna

ረዥምና የክርንን ጫፍ የሚፈጥር ከክንዱ አጥንቶች አንዱ።

ክትባት Vaccine

ከሞተ ወይም ከተዳከመ ቫይረስ ባክቴሪያ ተዘጋጅቶ አንዳንድ ተላላፊ በሽታዎችን ለመከላከል የሚዘጋጅ

ክትባት Inoculation

በሽታዎችን ለመከላከል ቫይረስን በሰውነት ውስጥ ማስገባት ምሳሌ፣ ፈንጣጣ

ክንድ Forearm

ከክርንና አንባር መሃከል ያለው የላይ ጅገር ክፍል።

ክንፈ አካል Limb

በቀኝ ወይም በግራ የላይ ወይም የታች ጅገር።

ኮሌራ Cholera

በተበከለ ምግብ ወይም መጠጥ አማካይነት አጣዳፊ የአንጀት ልክፈት። ዋናው ምልክቶቹም ከባድና አጣዳፊ ተቅማጥ፣ ትውከት፣ የጡንቻ መቀረጣጠም፣ የሽንት መጠን መቀነስና የሰውነት መድከም ናቸው። ዝማ

ኮምትሬ Cirrhosis

በልዩ ልዩ መርዛት ባክቴርያዎች ወይም በሌሎች ምክንያት በጉበት ላይ የሚደርስ ተዋረድ ለውጥ። የዚህ አይነት ለውጥ የሚታይበት ጉበት ለስላሳ መሆኑ ቀርቶ የተከማተረና የጠጠረ ይሆናል።

ኮፕሊክ ነጠብጣብ Koplick Spot

የኩፍኝ ቀዳ ምልክት ከመውጣቱ በፊት በጉንጭ ውስጥ የሚወጣ ነጣ ያለ ነጠብጣብ።

ወ

ወለምታ Sprain

በአደጋ መነሻ በመገጣጠሚያዎች ላይ የሚደርስ ጉዳት፣ መገጣጠሚያው ያብጣል፣ ያተኩሳል እንዲሁም ሲያንቀሳቅሱት ያማል።

ወሊድ ቁጥጥር Birth Control

በልዩ ልዩ ዘዴ እርግዝናን መከላከል።

ወላድ Multi gravida

ከሁለት ወይም ከዚያ በላይ የወለደች ሴት።

ወረራ Infestation

በጥቃቅንና በጥገኛ ህዋሳትና በተባይ የሰውነት መወረር።

ወረርሽኝ Epidemic

በአንድ ጊዜ ብዙ ሰዎችን የሚያጠቃ ተላላፊ በሽታ።

ወራጅ ደንዳኔ Descending colon

ከጣፊያ አካባቢ እስከሲግማእል ደንዳኔ ዱረስ በሆድ ግራ በኩል ቁልቁል የሚወርድ ደው የደንዳኔ ክፍል /የአንጀትን ስእል ተመልከት/።

ወረዝ Adolescent

በአቅመ አዳም /አቅመ ሄዋን/ መድረሻና በአዋቂነት መካከል ያለ ክፍለ ዘመን በወንዶች ከ14 እስከ 21 አመት ሲሆን በሴቶች ከ12 እስከ 19 አመት ድረስ ያለው የእድሜ ዘመን።

ወርች Arm

የላይኛው ጅግር አካል የሆነና ከትከሻና ከክርን መሃከል ያለው።

ወርች አፅም Humerus

ከትከሻና ከክርን መሃከል የሚገኝ ረጅም አጥንት።

ወር አበባ Mensturation

ከጉልምስና እስከ እርጣት ጊዜ ድረስ ከማህፀን የሚወጣ ፈሳሽ። ይህ ፈሳሽ ደም፣ የፈራረሰ የማህፀን ግለፈትና የማህፀን እጢዎች ፈሳሽ ይይዛል። የወር አበባ ፈሳሽ አይረጋም ነገር ግን የሚረጋ ከሆነ ደንበወጥ ነው።

ወስፋት Ascaris

ከክብ ትሎች ዘርያ የሆነ የአንጀት ትል።

ወባ በሽታ Malaria

አጣዳፊ አንዳንዴም የሚያቆም በወባ ትንኝ አማካይነት የሚመጣ በሽታ፣ ምልክቱም ወቅት በመለየት ብርድ ብርድ ማለት፣ ማንዘፍዘፍ፣ ማንቀጥቀጥ፣ ትኩሳትና ማላብ።

ወተት Milk

ህፃን የሚመገበው ከጡት እጢ የሚመነጭ ፈሳሽ፣ ውሀን፣ ኦርጋኒክ ለዩ ቁሶችን /ካርቦሃይድሬት፣ ፕሮቲንና ስብ/ እንዲሁም ሚኔራሉችን /ካልሲየም፣ ሶድየምና ፖታሲየም/ በተጨማሪም ለዩ ለዩ ቪታሚኖችን ከእናት ደም የተገኙ ፀረገዶ አካላ ትንና ኢንዛይሞችን የሚይዝ::

ወይባ Jaundice

በደም ውስጥ ቢላሩቢን በብዛት መጠራቀም ምክንያት የሀሞት ቀለም ሀመልሚሉ ቆዳን የአይን ነጩን የሰውነት ፈሳሾችን ወዘተ ቢጫ መልክ ሲሰጥ ይህም የሚደርሰው የሀሞት ቦዮች ሲዘጉ የቀይ ደም ህዋሳት በብዛት ሲፈራርሱ ወይም የጉበት ህዋሳት በደምብ ሳይሰሩ ነው::

ቀሺት Alveolus

ሀ/ ጥርስ በድድ ላይ የሚገባበት መሰኪያ፣ ለ/ በሳንባ ውስጥ ያሉ ጥቃቅን የአየር ከረጢቶች፣ ሐ/ የእጢ ሽክና::

ቀዘለ ቀለጥ Hydrolele

በማህደረ እስኪት ውስጥ ፈሳሽ ሲጠራቀም የሚደርስ እብጠት::

ውሃቋጠር Vesrcle

በቆዳ ላይ ትንሽ ፈሳሽ በመቋጠር ጉብ የሚል ከረጢት::

ውሃዘለ Edema

ፈሳሽ በህብረህዋስ በመጠራቀም የሚደርስ እብጠት:: እብጠቱ የደረሰበት አካል በጣት በተጫኑት ጊዜ ይሰረጉዳና ከጥቂት ጊዜ በኋላ እንደገና ተመልሶ የሚያ ሞላ፣ በተለያዩ የልብ የጉበትና የኩላሊት በሽታዎች ሊያጋጥም ይችላል::

ውልቀት Dislocation

የአጥንት ከመደበኛ መጋጠሚያው መውጣት ወይም መቃወስ::

ውርስ Inherited

ከዘር ወይም ከወላጆች የተገኘ::

ውስጠ Intra

በውስጥ ለማለት ባእድ መነሻ ምሳሌ፣ ውስጠ ማህፀን በማህፀን ውስጥ::

ውስጠመግል Empyema

በገበር ወይም በሃሞት ከረጢት ውስጥ የመግል መጠራቀም::

ውስጠማህፀን Endometrium

የማህፀንን ውስጥ የሚሸፍን ለፋጭ /ንፋጭ/ መሰል ለባስ::

ውስጠእመንጪ እጢ Endocrine gland

ሆርሞናቸውን በማፍለቅ ቀጥታ ወደደም ለሚያፈሱ እጢዎች የተሰጠ አጠቃላይ ስም:: ለምሳሌ እንቅርት እጢ፣ እንቁልጢ ኩሊትን እጢ ወዘተ...

ውስጣዊ Internal

በሰውነት ውስጥ በውስጥ ወይም ወደ ውስጥ የውጫዊ ተቃራኒ::

ውስጣዊ መርዝ Endotoxin

በጥቅንአካል ወይም ባክቴርያ ውስጥ የሚዘጋጅ መርዝ። ባክቴርያው በሚፈራርስ በት ጊዜ የሚወጣ።

ውስጥ ሎምብ Labia Minora

በሴት ብልት መግቢያ ግራና ቀኝ የሚገኝ ስስ የሆነ የቆዳ እጥፈት ከውጭ ሎምብ በስተውስጥ የሚገኝ።

ውስጠ ደዌ ህክምና Medicine

ያለቀዶ ህክምና በመድሃኒቶች በሽታን ማከም።

ውጫዊ ዘርአባል External genitalia

በውጭ በኩል በግልፅ የሚታየው የወንድ ወይም የሴት ብልት ክፍል።

ውጫዊ ጆሮ External ear

ውጭውና የጆሮ ቅጠልና የመስሚያን ቱቦ እስከጆሮ ከበሮ ድረስ ያለው ክፍለአካል የሚያጠቃልል መጠሪያ /የጆሮን ስእል ተመልከት/።

ውጭ ሎምብ Labia Majora

በሴት ብልት መግቢያ ግራና ቀኝ በስብ ህብረህዋስ የተሰራ።

ውጭ እስትንፋስ Expiration

ወደውጭ መተንፈስ፣ እስትንፋስን ወደውጭ ማስወጣት።

## ዘ

ዘረንጉዳይ Fungus

አነስተኛ የእፅዋት ዘር የሆነ እንደእንጉዳይና የመሳሰሉትን የሚያጠቃልል፣ አንዳንዶቹ በሽታን ያመጣሉ።

ዘራይጥ Rodent

የአይጥ ዘር ነት ያለውና በመጉርደም ወይም በመጋጥ የሚመገብ እንስሳ ምሳሌ፣ ጥንቸል።

ዘር አባል /ዘራባል/ Genitalia

የመራቢያ አባላካላት አጠቃላይ መጠሪያ።

ዘርአባል ሽንታውጪ ቅንባር Genitourinary system

የመራቢያ አባላካላትንና ሽንት አፍላቂ አባላካላትን ያጠቃለለ ክፍለአካል።

ዘርጊ Extensor

አንድን ክፍለአካል የሚዘረጋ ጡንቻ።

ዘበመአከል Medial

ወደ ሰውነት ማእከላዊ መስመር ቀረብ ያለ።

ዘንግ ነርቭ Axon

ከነርቭ ህዋስ አካል ጀምሮ ነርቩ እስከሚያገለግለው አባላካል መጨረሻ ያለው የነርቭ ጭረት።

ዝለፍታ /ሾክ/ Shock

በመድማት በመቃጠል ወይም ለከፈት ወዘተ... ምክንያቶች የደም ግፊት መውረድና የሰውነት ህዋሳት የኦክስጂን መድረስ።

